# ኢትዮጵያ

## የባሩድ በርሜል



ሮማን ፕሮቻዝካ

ትርጉም በደበበ እሸቱ

# ኢትዮጵያ
## የባሩድ በርሜል

የወቅቱ አንገብጋቢ ጉዳይ

~ 1935 (እ.አ.አ) ~

በሮማን ፕሮቻዝካ (ባሮን)

ትርጉም በደበበ እሸቱ



# ማውጫ

# የአሳታሚው ማስታወሻ

መላው የአፍሪካ አህጉር በአውሮፓውያን የከፋ የቅኝ አገዛዝ ስር ወድቆ በሚማቅቅበት ዘመን ኢትዮጵያ ወራሪውን የጣሊያንን መንግሥት በአፄ ምኒልክ መሪነት በማሸነፏ በአውሮፓውያን ቅኝ ገዢዎች ጥርስ ገባች። በቅኝ ግዛት ከፍተኛ በደል ለሚደርስባቸውና በባርነት ለሚማቅቁ ሕዝቦች ደግሞ የተስፋ ብርሃን ፈነጠቀች፤ ተምሳሌትም ሆነች።

የኢትዮጵያ ሕዝብ እንደቀድሞው ሁሉ ጀግንነቱን አድዋ ላይ በዓለም ፊት ከአስመሰከረ በኋላ የኢጣሊያኖቹ ክህደት፣ ድፍረትና ወረራ እንዳይደገም በማሰብ በአውሮፓውያን ላይ ተጠራጣሪነቱ ጨመረ፤ "አትንኩኝ" ባይም ሆነ።

ለሥራ ወደ ኢትዮጵያ የሚመጡ ፈረንጆችም ቅኝ ተገዢ ከሆነው ከሌላው የዓለም ሕዝብ የሚያገኙትን ክብርና ታዛዥነት በማጣታቸው እንደዚህ መጽሐፍ ደራሲ ያሉ ጥቂቶች መከፋታቸውና ለብቀላ መነሳሳታቸው፤ ብሎም ኢትዮጵያውያንም እንደሌላው የቅኝ ተገዢ ሕዝብ የበታችነት ስሜት እንዲያድርባቸው ለማድረግ ሌት ተቀን ማሴራቸውን በሰፊው ተያያዙት።

ሀገራችን ለምን ጥርስ ውስጥ ገባች? በፋሺስት ጣልያን ወረራ ጊዜ ለምን የአፄ ኃይለ ሥላሴን አቤቱታ ብቸኛ አፍሪካዊ አባል የነበሩበት የመንግሥታቱ ማኅበር አልሰማ አለ? የዚህንና የሌሎች አንገብጋቢ ጥያቄዎች መልስ ለማግኘት አንባብያን በየመጽሐፍቱ ገፆች ፊት ለፊታችን የተደበቁትን ምሥጢሮች ማሰስና መፈተሽን ይጋብዛል።

የጊዜውን የቅኝ ገዢዎች መላ ፍንትው ብሎ ያመላከተውንና በዘረኛው ጠበቃ በሮማን ፕሮቻዝካ በ1935 (እ.አ.አ) መግቢያ ላይ በጀርመንኛ ቋንቋ ተደርሶ በኦስትሪያ፣ በዓመቱ መጨረሻ ላይ በለንደን ከተማ በእንግሊዙ ዓለም አቀፍ የዜና አገልግሎት በእንግሊዝኛ ቋንቋ የታተመው ይህ መጽሐፍ እነሆ በእውቁ ከያኒ ደበበ እሸቱ ወደ አማርኛ ቋንቋ ተመልሶ ለመጀመሪያ ጊዜ ለንባብ ቀርቧልና የአንባብያንን ጥያቄዎች ለመመለስ እንደሚረዳ ተስፋ እናደርጋለን።

የእንግሊዝኛው መጽሐፍ ዕትም ላይ የሰፈረው የአሳታሚው መቅድም ጽሑፍ "የመጽሐፉ ደራሲ እስከ 1934 ዓ.ም ድረስ በአዲስ አበባ በሚገኙ የተለያዩ የዲፕሎማቲክ ስብሰባዎችና በአውሮፓውያን የቆንስላ ልዩ ፍርድ ቤቶች በተለያዩ ጉዳዮች ላይ ሲማጸን የነበረ ጋዜጠኛ ነው" ይለዋል። "የኢትዮጵያን ውስጣዊ አስተዳደር በተመለከተ ያሰፈረው ዘገባ የጦርነቱን መቃረብ ከታማኝ ምንጮች ያረጋገጠ መሆኑን[ም] ያስረዳል። በቅርቡ የታዩትን ወቅታዊ

ሁኔታዎች አስመልክቶ ያነሳቸው ነጥቦች ተአማኒ በመሆናቸው ፍራቻውና መላ ምቱ ትኩረት ሊቸራቸው ይገባል።" ሲልም ያስጠነቅቃል።

ከሰማንያ ዓመታት በኋላ ደግሞ በዚህ "በባሩድ በርሚል" ፍንዳታ ያልፈራረሰችና በመላ ምቱም መርዝ ያልጠፋች "ጉደኛ" አገር ዜጎች ለመጀመሪያ ጊዜ የዚህን መጽሐፍ ምስጢር በራሳችን ቋንቋ አንባቢ እንሆናለን።

ምንም እንኳን ገና የፋሺስት ጣልያን አገራችንን ሳይረግጥ ደራሲው አውሮፓውያን በአፍሪካ ውስጥ ያላቸውን ዘላቂ ፍላጎት ለማጠናከር ኢትዮጵያ በአፍሪካዊያን ላይ ያላትን ተጽእኖ ማኮላሸትና ኢትዮጵያን በአውሮፓውያን አገዛዝ ስር ለመጣል ብቸኛው ምርጫ 'የኢትዮጵያን ሕዝቦች በነገድ፣ በዘር፣ በቋንቋና በባህል መከፋፈል ነው' ሲል በመጽሐፍ አሳትሞ በአውሮፓ ከተሞች አሰራጨ። ይህ መርዝ ታዲያ በሰዓት እንደሚሞላ ቦምብ ወቅትና ትውልድ እየጠበቀና እየመረጠ ሲፈነዳ እየመሰከርን ነው። ይህ ታዲያ ማርከሻ ያስፈልገዋልና አንባብያን ተወያይተውና ተማክረው ዘር፣ ኃይማኖት፣ ጾታና እድሜ ሳይለያቸው ለሀገራችን ትንሳዔ ማርከሻውን መላ ምት በጋራ እንደሚሹ እናምናለን።

ይህ ለመጀመሪያ ጊዜ በአማርኛ የታተመው መጽሐፍ የሚያስተምረን ምን ያህል አደገኛ መርዝ የተቀመመልን መሆኑን ነው። እንደዚህ አይነቶቹን መረጃዎች በአግባቡ ከተጠቀምንና ያለፈውን ታሪካችንን አስታውሰን መጥፎው እንዳይደገም፣ መልካሙ ደግሞ ይበልጥ እንዲጎለብት ካደረግን ለታቀዱልን የአንድነት ፈተናዎች ሁሉ መፍትሔ ማግኘት እንችላለን።

በአንድነትና በሰላም የሚኖር ትውልድና የተሻለ አገርም ለመፍጠር በጋራ እንሥራ፣ ሳንጠባበቅ የየበኩላችንን ከማድረግም አንቆጠብ፣ ከሁሉም በላይ አንድነታችን የሚያሸብራቸው የጠላቶቻችን መሳሪያ እንዳንሆን እንጠንቀቅ፣ ተግተንም ለአንድነታችንና ለትንሳዔያችን እንሥራ።

በዚህ አጋጣሚ ለተርጓሚው ለአቶ ደበበ እሸቱ፣ ይህን ሀገራዊ ተልዕኳችንን ለማሳካት ላስቻሉን ለመላው የፀሐይ አሳታሚ ድርጅት ደጋፊ፣ ተባባሪና አንባቢ ወገኖቻችንን፣ እና ባልደረቦቻችንን ሁሉ የከበረ ምስጋናችን ይድረሳችሁ።

ኤልያስ ወንድሙ
የካቲት 2007 ዓ/ም
ሎስ አንጀለስ

# የተርጓሚው ማስታወሻ

ቀደም ሲል ስለ ኢትዮጵያና ኢጣሊያን ጦርነት በተለያዩ ውይይቶችና አጋጣሚዎች እሰማ የነበረ ቢሆንም በዚሁ ርዕስ ጉዳይ የተዘጋጀውን መጽሐፍ አግኝቼ ማንበብ አልቻልሁም ነበር። እንደ አውሮፓውያን አቆጣጠር በ2002 ወይም ሶስት ላይ አንድ ጠዋት የእንግሊዙን ዜና ማሰራጫ ተቋም (ቢቢሲ) የሬዲዮ ስርጭት ሳዳምጥ ተቋሙ መጽሐፍ ማሳተሙን አስመልክቶ ትንታኔ ሲሰጥና በመጽሐፉ ላይ ውይይት ሲደረግበት ሰማሁ። ስርጭቱ ከተጀመረ ስለደረስሁ ነገሩ ትንሽ ግራ አጋባኝና ምናልባት የጸሐፊውን የትውልድ ቀን ወይም የሞተበትን ጊዜ ለማሰብ የተደረገ ዝግጅት ይሆናል ብዬ አሰብሁ።

ውይይቱ ሲቀጥል ግን ያሰብሁት አልሆነም። እንዲያውም በመደምደሚያው ላይ "የመጽሐፉ ደራሲ ያነሳቸውና እንደማሳሰቢያ ያሠፈራቸው ጉዳዮች በኢትዮጵያ ውስጥ ጊዜ ጠብቆ እንደሚፈነዳ ቦንብ ሆነዋል" በማለት ሲነገር መጽሐፉን የማግኘትና የማንበብ ፍላጎቴ በረታ።

መጀመሪያ ያገኘሁት መጽሐፍ አንድ ገጽ ጎድሎት ነበር፤ በአሜሪካ ነዋሪ የሆነው አብሮ አደግ ጓደኛዬ ጌታቸው አድማሱ ሙሉ መጽሐፉን ላከልኝና አነበብሁት።

አንድ ዕለት ከወዳጄ ነፃነት ክፍሌ ጋር ስለዚሁ መጽሐፍ አንስተን ስንነጋገር የቢቢሲን ውይይት እንደሰማውና በአሁኑ ጊዜ ለምን እንደቀረበ ግራ መጋባቱን አንስቶ ረጂም ጊዜ ተነጋገርንበት። በዚህ ዕለት ነው መጽሐፉን ኢትዮጵያውያን ሁሉ ማንበብና ሁኔታዎችን ማገናዘብ አለባቸው ብዬ የወሠንሁት።

ጸሐፊው ኢትዮጵያ ላይ ካለው የመረረ ጥላቻና ዘረኝነት በመነሳት "ኢትዮጵያ" የምትባል ሀገርና "አማራ" የሚባል ሕዝብ እንዲጠፉ፤ ኢትዮጵያ በዘር፣ በቋንቋና በሀይማኖት ተከፋፍላ ብትንትኗ እንዲወጣ በከፍተኛ ደረጃ አሲሯል። ከጃፓን ጋር ግንባር የፈጠረች አደገኛ አገር መሆኗን በማስገንዘብም ጥላቻውን በሚገርም ሁኔታ ገልጧል። ወደ ዓለም ማኅበርም (ሊግ ኦፍ ኔሽን) "ይህች ሥልጣኔ ያላያት፣ ዕድገት የምትጠላና የባሪያ ንግድ የምታካሂድ ሀገር አባል ልትሆን አይገባትም፤ ወጣቶቿዋ የሠለጠነው ዓለም በሚቸራቸው የትምህርት ዕድል ተጠቅመው ትምህርታቸውን ካጠናቀቁ በኋላ የሠለጠነውን ዓለም ለማጥፋት የሚጥሩ ናቸው" የሚል መርዝ የረጨ ክፉ ጠላት ነው።

የኢትዮጵያንና የኢትዮጵያውያንን ጠላት ሁሉም እንዲያውቀው "በዚያ ቀውጢ ወቅት ማን አብሮን ቆመ? ማን በጠላትነት ተሰልፎ ነበር? ወዘተ" የሚለውን ቁምነገር ትውልድ ሁሉ ሊያውቀው ስለሚገባ ለመተርጎም ወሠንሁ።

ስለሃገራችን በተለያዩ ዘመናት በርካታ ተመራማሪዎችና የታሪክ ጸሐፍት በተለያዩ ርዕሰ ጉዳዮች ላይ ጽፈዋል። ይህን ለማድረግም ሀገር አቋርጠው፣ ረጂምና ያልሠለጠነ መንገድ ተጉዘዋል። እነዚያ መጻሕፍት ደግሞ ከሀጋራችን አልፈው በተለያዩ የዓለም ክፍሎች ባሉ አብያተ መዛግብትና አብያተ መጻሕፍት በጥንቃቄ ተይዘው ታሪክ እየዘከሩ፣ ኢትዮጵያን እያስተዋወቁና ለብዙ ትውልድ እያስተማሩ እስካሁንም አሉ።

እግር ጥሎን፣ ወይም እድሉ ገጥሞን ከሀገር ወጥተን ሌሎች አገሮችን ጎብኝተን በሰው ሀገር ከተደረደሩ ታሪካዊ መጻሕፍት ስለሀገራችን ማንበብና ማወቅ የበቃን ስንቶቻችን እንደሆንን ፈጣሪ ይወቅ። እንዳለመታደል ሆኖ የራሳችንን ታሪክ በውጭ ቋንቋ ብቻ በማንበብ ዘመናት አልፈዋል። በተለያየ አጋጣሚ ከሀገር ወጥተው ኑሯቸውን በውጭ ያደረጉ ኢትዮጵያዊያንም ቢሆኑ ከሚገጥማቸው የኑሮ ፈተና የተነሳ የኛን ማንነት ፍንትው አድርገው የሚነግሩንን፣ ወዳጅ ጠላታችንን የሚያሳውቁንን እነዚያን ጥራዞች መተርጎምና ለንባብ ማብቃት ቀርቶ ለራሳቸውም የማንበቢያ ጊዜ የላቸውም።

ጊዜ መልካሙ ይህን ክፍተት እንዲሞላ በምክንያት ከሀገሩ የወጣውን የፀሐይ አሳታሚን ድርጅት ፈጥሮልን በርካታ መጻሕፍትን ለማንበብ አብቅቶናል። ሰው ከተወለደበት፣ ካደገበትና ከኖረበት ሀገሩ በመውጣቱ "እንኳን ተሰደደ" ባይባልም እኔ ግን አቶ ኤልያስን እንኳንም ወጥተህ ይህን ድርጅት ለማደራጀትና እኛ ያጣነውን፤ ትውልዱ ግን ሊያውቀው የሚገባውን የሀገሩን እውነታ ለማሳወቅ ቻልህ ማለት እደፍራለሁ። የቁጭቴ መወጫ ትርጉም ለመነበብ የበቃው በፀሐይ አሳታሚ ድርጅት መኖር ነውና። ኢትዮጵያ ምንጊዜም ቢሆን የጎደለባትን የሚሞላ፣ ያጣችውን የሚያስገኝላት፣ የናፈቀችውን የሚያቀርብላት አምላክ አላትና በፀሐይ አሳታሚ ድርጅት ገና ብዙ ያላወቅናቸውን እናውቃለን።

ደበበ እሸቱ
ኅዳር 2007 ዓ/ም
አዲስ አበባ

# መቅድም

ይህ መጽሐፍ በአብዛኛዎቹ አንባቢዎች ዘንድ ኢትዮጵያን የሚቃወም መስሎ ሊታይ ይችላል፤ ጸሐፊው ይህን በአግባቡ ቢገነዘብም ኢትዮጵያን በመደገፍ በተደጋጋሚ የወጡትንና የሚወጡትን ጽሑፎችና ሕትመቶች መቃወም አስፈላጊ መሆኑን ያምንበታል። በዓለም ማኅበር ውስጥ የተካተቱትን አባል አገሮች በዕኩል ደረጃ መመልከት ምንም ያህል አስፈላጊ ቢሆንም በጥንቃቄ ሊጤን የሚገባው ጉዳይ ግን አለ። ኢትዮጵያ አሁን ያለችበት ሁኔታም ሆነ ለተከታዮቹ በርካታ ዓመታት ለመልማትና በራሷ ፖሊሲ ለመመራት ችሎታው ጨርሶ የሌላት ሀገር ናት።

ይህን እንድታደርግ ማደፋፈሩና መርዳቱ የሠለጠኑትን ዓለማት ፍላጎት የሚያዳክምና የዓለማችንን የተረጋጋ ሰላም የሚያቃውስ ነው። ከዚህ በተጨማሪ የኢምፔሪያሊዝም ተቀናቃኞችም ቢሆኑ ሊገነዘቡት የሚገባው እውነታ አማርኛ ተናጋሪ ያልሆኑትና አብላጫ ቁጥር ያላቸው ሌሎች የሀገሪቱ ዜጎች የኢትዮጵያ ኢምፔሪያሊዝም ተጠቂዎች መሆናቸውን ነው። ስለዚህ አለአግባብ ዙፋኑ ላይ የተቀመጡትን ኢትዮጵያውያን "ለጭቆና ተዳርገዋል" በማለት ማንኛውንም ድጋፍ መስጠት አግባብነት የለውም።

ጸሐፊው ቀደም ሲል በ1935 በጀርመን ባሳተመው የመጀመሪያው መጽሐፉ ከላይ ያነሳቸው ነጥቦች በሂደት የተረጋገጡ ናቸው። የወደፊት ሥጋቱን በተመለከተ ቢያንስ በዚህኛው ላይ ያነሳቸው ፍርሃቶች ትኩረት ሊሰጣቸው ተገቢ ነው።

የእንግሊዝ ዓለም አቀፍ የዜና አገልግሎት
1935
ለንደን




የኢትዮጵያ ካርታ - 1906

# ፩

# በኢትዮጵያ ውስጥ የሚካሄደው ምንድን ነው?

ከአውሮፓ በ3000 ማይልስ ርቀት ላይ በጨለማው (የአፍሪካ) አህጉር በስተምስራቅ በኩል ሥርወ መንግሥታቸውን ከአዋቂውና ጥበበኛው ንጉሥ ሰሎሞን የሚያጣቅሱ ነገሥታት የሚገዟት፣ ከ1935 ጀምሮ በአፍሪካ ብቸኛዋ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆነችው ኢትዮጵያ ትገኛለች።

ለመሆኑ ይችን ሀገር በድንገት ወደዓለም አቀፍ ፖለቲካዊ መድረክ ያስገባትና ለእንዲህ አይነት ክብር ያበቃት ምክንያት ምንድን ነው?

ካለፉት አራት ዓመታት ጀምሮ በአዲስ አበባ የሚገኘው የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት የውጭ ፖሊሲውን በአውሮፓውያንና በአሜሪካ ላይ በሥራ ለመተርጎም እየተንቀሰቀሰ ነው። ከጃፓን ጋር በፈጠረው ጥብቅ ቁርኝት በሚያገኘው ትብብር በመታገዝ ከነጩ ዘር ጋር የሞት የሽረት ትግሉን ጀምሯል። ይህ ድርጊቱ በቸልታ ከታለፈ አደገኛነቱ ከመጠን ያለፈ ይሆናል።

ጥቃቱ ከኢትዮጵያ ግዛት አልፎ ወደ አካባቢው አዋሳኝ አገሮች ተሸጋግሯል። በዚህ ጥናት ሁለተኛው ክፍል ላይ የጥላቻው ማሳያ በዝርዝር ተገልጧል።

በዚህ የጥቃት ዕቅድ ውስጥ ተጠቂዎቹ በአፍሪካ የሚገኙ ሁሉም የቅኝ ገዢ ኃይሎች ናቸው። በማስረጃነት የምናቀርበውም በኢትዮጵያና በኢጣልያ መሀል የሚካሄደውን ሀገራዊ የድንበር ግጭት ነው። ጣልያኖች በሰሜን ኤርትራ፣ በደቡብ ምሥራቅ በሶማሊያ ባሏቸው የቅኝ ግዛት አገሮቻቸው ሳቢያ የኢትዮጵያ አጎራባች ናቸውና በዚህ አቅጣጫ በአውሮፓውያን ላይ የሚሰነዘረውን ጸረ ቅኝ ገዢነት ጦርነት ለመከላከል የቅድሚያ እርምጃ ሊወስዱ ይገባቸዋል።

በኢትዮጵያ መንግሥት የሚደገፈው የወጣት ኢትዮጵያውያን ንቅናቄ በዘዴና በጽናት እየተንቀሳቀሰ፣ በእያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ ኀሊና ውስጥ በነጭ ዘር ላይ ጥላቻን እየዘራ፣ አውሮፓውያን የሚለግሱትን ችሮታ በመጠቀም

ራሳቸውን አውሮፓውያኑን የቅኝ ግዛት ባለቤትነት ለማሳጣት በመንቀሳቀስ ላይ ነው። አውሮፓውያን ለጥቁሮች የዘረጉት የትምህርት ስርዓት መርዛማ ፍሬም እያፈራ ነው። የሀገሪቱ ዜጎች ለሕግ የማይገዙና በሥርዓት የማይመሩ በመሆናቸው ቅኝ ገዢዎች ለጉዳዩ ትኩረት በመስጠት ማንኛውንም ራስን በራስ የሚያስተዳድር መንግሥት አደገኛ አዝማሚያ ሊቆጣጠሩ ይገባል።

እንደ ኢትዮጵያ መንግሥት ግምት የኢትዮጵያ ግዛት ከ10 እስከ 12 ሚሊዮን የሚደርሱ ጥቁር ሕዝቦች የሚኖሩበት፣ የጀርመንን ግዛት ሁለት እጥፍ የሚሆን ሀገር ነው። በአንድ አቅጣጫ ከምስራቅ አፍሪካ እስከ ሱዳን፣ በሌላ አቅጣጫም ከሱዳን እስከ ኮንጎ ሲያካልል፣ በስተሰሜን ከጣልያን ቅኝ ግዛት ኤርትራ፣ በስተምስራቅም ከፈረንሳይ፣ እንግሊዝና ኢጣልያ ቅኝ ሀገር ሶማሌላንድ፣ ኬንያ፣ ከእንግሊዝ የሞግዚት አስተዳደር ኡጋንዳ፣ በደቡብም ከእንግሊዝዋ ቅኝ ግዛት ሱዳን ጋር ይዋሰናል።

የባህር በር የሌላት ሀገር እንደመሆኗ ኢትዮጵያ የውጭ ንግዷን ለሌላው ዓለም ለማስተላለፍ የምትጠቀመው ዋና ከተማዋን አዲስ አበባን ከጅቡቲ ጋር በሚያገናኘው በፈረንሳይና ኢትዮጵያ የምድር ባቡር ኩባንያ ነው። ይህም በፈረንሳይ ሶማሌ ላንድ ክልል ላይ የሚያልፍ የ500 ማይልስ ርቀት አለው። በ1935 ሮም ላይ በፈረንሳይና በጣልያን መንግሥታት መሀል በተደረሰው የቅኝ አገዛዝ ስምምነት መሠረት የዚህ ምድር ባቡር አብዛኛው መብት ያለው በጣልያን መንግሥት እጅ ነው።

ወደ አዲስ አበባ የሚገቡት ሁለቱ የቴሌግራፍ መስመሮች የሚተዳደሩት በውጭ አስተዳደር ነው። የሐዲድ መስመሩን ተከትሎ ያለው የፈረንሳይ ሲሆን በሰሜን አቅጣጫ የሚገኘው የኤርትራ ድንበር ግን የኢጣልያ ግዛት ነው። ከዚህ ውጪ ያለውና አሮጌው የንግድ ጉዞ መስመር በበጋ ወቅት ካልሆነ በቀር ለመኪና መተላለፊያነት የማያገለግል ያልሰለጠነ መንገድ ነው። የሀገሪቱን አጠቃላይ እንቅስቃሴ የሚያስተናግዱትም እነዚሁ መንገዶች ናቸው።

ለውጭ ገበያ የሚዘጋጁት ጠቃሚ ምርቶች ለራሳቸው ለኢትዮጵያውያንም ሆነ ለአውሮፓውያን የኤኮኖሚ ጠቀሜታ የግድ የባህር በር ያስፈልጋቸዋል። ለውጭ ገበያ የሚያቀርቡት ዋና ምርት ቡና ሲሆን ቆዳ፣ የቆዳ ውጤቶች፣ ወርቅ፣ ፕላቲኒዩም፣ በእጅጉ ተፈላጊነት ያለው የማይካ ንጥረነገር መኖሩ ይነገራል። ከሁሉም በላይ የነዳጅ ዘይት አለ ተብሎ በመታመኑ ሀገሬዎቹ በአካባቢው ምንም አይነት ነዳጅ ቢቀጣጠል ከፍተኛ እሳት ይነሳል ብለው ይፈራሉ። በሐበሻ ምድር በርበሬ ከመመረቱ ሌላ ዝባድ የሚገኝበት ብቸኛ ሀገር ነው።

ኢትዮጵያን ከመካከለኛው አፍሪካ ተመራጭ የሚያደርገው ዋና ከተማው አዲስ አበባ በተራራማ አካባቢ የሚገኝ በመሆኑ ተወዳጅ የዓየር ጠባይ እንዲኖረው ማድረጉ ነው። ደጋማው የሀገሩ ክፍል ከትኩሳት በሽታ፣ ከወባ፣ ከቢንቢና ከእንቅልፍ ትንኝ የጸዳ ነው። ከምድር ሰቅ በአምስት ዲግሪ ርቀት ላይ የሚገኝ በመሆኑም የዓየሩ ጠባይ ተመጣጣኝና ለአውሮፓውያን ተስማሚ

ነው። ኢትዮጵያን የቀን ተቀን የፖለቲካ ማዕከል ያደረጋት የአውሮፓውያን የቅኝ ገዢነት መስፋፋት ጉጉት ሳይሆን የሀገሬው ዜጎች በዓለም ላይ ካለው የኢኮኖሚ ሁኔታ ጋር ለመጣጣም ያላቸው ፍላጎት፣ ስለሰላም ያላቸው ምኞትና አውሮፓዊ ሥልጣኔ ነው።

# የአፍሪካ ሥጋት

በኢትዮጵያ መንግሥት አስተዳደር ላይ የሚታየው አሳዛኝ ጉድለት በሀገሪቱ የኤኮኖሚና የባህል እድገት ላይ እስካሁን ያሳደረው ተጽእኖ ነው። ገዢው የአማራ ብሔር ለውጭ ኃይሎች ያለው ጥላቻ ለሁሉም የውጭ መንግሥታትና ዜጎቻቸው አሳሳቢ ሆኗል። ከጊዜ ወደ ጊዜ የሚሰጠው ዋስትና እርስበርሱ የሚቃረን ነው። በውጭ አገሮች በመታተም ላይ ያሉት ሐተታዎችና መግለጫዎች ሆን ተብለው የሕብረተሰቡን አስተሳሰብ ለማዛባት የሚረጩ ናቸው። በተቻለ መጠን የውጭ ኃይላትን በማዳከምና ተሥፋ በማስቀረጥ በኢጣልያ ባለአደራነት በውጭ ኃይሎችና በኋላም በልባሙ ንጉሥ ምኒልክ ለሀገሬውና ለነጮች የለሙትንና የተደራጁትን የአውሮፓ ተቋማት ለማጥፋት የተቃጣ አካሄድ ነው።

የኢትዮጵያ ሕዝቦችና ነገዶች በዘር፣ በቋንቋ፣ በባህል ከኢትዮጵያ ገዢዎች ጋር ራስን በራስ የማስተዳደር መብት ተሰጥቷቸው ቢሆን ኖሮ ገና ድሮ የኢትዮጵያዊነትን እስኳል ከውስጣቸው አውጥተው በጣሉ ነበር። ሁኔታው ግን ከዚህ የተለየ ነው። ከአውሮፓውያን ተሰሚነትና ተራማጅ አስተሳሰብ በተቃራኒ ለራሳቸውና ለሀገራቸው ሊያስገኝላቸው ከሚችለው ጥቅምና ግንዛቤ አራርቀው በተጽእኖ እየገዟቸው ነው።

ኢትዮጵያውያን ጥረታቸው ከዚህ የላቀ ተግባር ማከናወን ነው። በነጭ ዘር ላይ ባላቸው የጥላቻ ፖሊሲያቸው የመጨረሻው ግባቸው ከጃፓን ጋር በተስማሙበት የዕርዳታ ውለታ በመተማመን ከአፍሪካውያን ሁሉ የተሻሉ ሆነው መታየት ነው። የኢትዮጵያ ሕዝቦች የሚያስከትለውን መዘዝ ባለማወቅ ወይም የኃላፊነቱን ከባድነት ባለመገንዘብ ወደ አስከፊ ጀብደኝነት ለመግባት ጠርዙ ላይ ናቸው።

የኢትዮጵያው ንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴ በሰኔ 1935 ለብርቱዎቹ የጦር አለቆቹ ባደረገው ንግግር የሚከተለውን አባባል ተጠቅሟል፡-

> የአፍሪካ ብቸኛ ንጉሥ እኔ ነኝ፤ የዓለም ጥቁር ሕዝቦች (ገና ነጻ ያልወጡትን ጨምሮ) መሪ እኔ ነኝ... አውሮፓውያንን በመላ ልናያቸው የሚገባን እንደውጪ ሰዎች ብቻ ሳይሆን እንደጠላትም ነው።

ከጥቂት ቀናት በኋላም "ለ ማተን" የተባለው ጋዜጣ ላደረገለት ቃለ መጠይቅ ንጉሡ ከየመን፣ ከሂጃዝ እና ከግብጽ ጋር ስላለው የጠበቀ ወዳጅነት ሲናገር፡-

በቁርአን ላይ ሞሐመድ እንዳሰፈሩት ኢትዮጵያዊያን አስተናግደውኛል ብለዋል። ስለዚህ አስፈላጊ በሚሆንበት ጊዜ ሁሉ ሙስሊሞች ኢትዮጵያን ሊረዱ ይገባቸዋል።

እነዚህ አዋጆች በኢትዮጵያ ከፍተኛ ባለሥልጣን ሲተላለፉ የሁሉም የሀገሬው ተወላጅ፣ ከኢትዮጵያ ወሰን ባሻገር ያሉትን ጨምሮ ንጉሡን እንደመሪያቸው እንዲቀበሉና ከነጮች ጋር በሚደረገው ፍልሚያ ከጎኑ እንዲሰለፉ ሚዛኑን ለማስተካከል የታቀደ ነው። በአካባቢው የተመሠረተውን የቅኝ አገዛዝ መሠረት በማናጋት የራሱን የገዢነት መንበር በማጠናከር በአፍሪካ በቅኝ ገዢነት ያሉት ኃይሎች በገዥነት የመቆየት ዕድላቸው አደገኛ አዝማሚያ እያጋጠመው ነው።

# ኢትዮጵያውያን በመንታ ጎዳና ላይ

የኢትዮጵያ መሪዎች በዓለም ታሪክ ላይ ጠባሳውን ትቶ የሚያልፍ ታሪክ ለማስመዝገብ ጉዞ ጀምረዋል። አሁን መምሪፕ ያለባቸው አውሮፓውያን በአፍሪካ ውስጥ ባላቸው ተሰሚነት ውስጥ በመካተት በፈቃደኝነት ለሚካሄደው ባህላዊ ልማት እና ሥልጣኔ ታማኝ ተባባሪ መሆን፣ ወይም በማይረባ ቅሬታ እና በተቃወሰ የዘር ጥላቻ መላ ቢስ የሆነውን ፖሊሲ በነጭና በጥቁር ሕዝቦች መኻል የጥላቻ እሳት በማቀጣጣልና ዓለም አቀፉን ሕዋ (ሁኔታ) በመበከል በመካሄድ ላይ ያለውን ሰላማዊ የሥልጣኔ ሂደት ማኮላሸት ነው።

የዚህ ጥናት ዋነኛ ትኩረት አስጊ ስለሆነው ክስተትና በነጩ ሕብረተሰብ ላይ የሚካሄደውን የጥላቻ ዘመቻ በዚህ በ11ኛው ሰዓት ላይ በጽሑፍ በተመሠረተ ማስረጃ የታገዘ ማስጠንቀቂያ መስጠት ማስፈለጉን ማስገንዘብ ነው።

በኢትዮጵያ ዋና ከተማ ለሁለት ዓመታት ስኖር ልዩ በሆነው ጥምር ፍርድ ቤትና በውጭ መንግሥታት የቆንሲላ ችሎቶች አቅሜ በፈቀደልኝ ሁሉ ጠበቃ በመሆን ከመቶ የማያንሱ የሁሉንም ነጭ ዘሮች መብት በማስጠበቅ፣ በኢትዮጵያ መንግሥት የተወላገደውን ፍርድና በሀገሬው ባለሥልጣናት የሚካሄደውን ሕገ ወጥ ድርጊት በመሞገት አደጋ በበዛበት ሥራ ላይ ነበርሁ። በነዚህ ጉዳዮች ላይ ያስመዘገብሁት የድል ውጤት ሁሉም ቆንሲላዎችና ዲፕሎማቲክ ሚሲዮኖች በአግባቡ እንዲቋቋሙ አድርጌያለሁ።

በኢትዮጵያ ባሉት አውሮፓውያን ላይ የሚደርስባቸውን /በገንዘብም ሆነ በፖለቲካ/ በደልና ግፍ በጄኔቫ ለሚገኘው የዓለም መንግሥታት ማኅበር ቢሮ በማመልከቴ "በሀገሪቱ የውስጥና የውጭ ደኅንነት ላይ ታሴራለህ" በሚል ውንጀላ በጥር 1934 የኢትዮጵያ መንግሥት ከሀገር እንድወጣ ወሰነብኝ። ይህም ለቆምሁለት ዓላማ ያካሄድሁት ሙግት ምንኛ የተሳካ እንደሆነና የኢትዮጵያም መንግሥት የሚያካሂደውን ሕገወጥ ተግባር በምንም መልኩ እንዲታወቅ ያለመፈለጉን በገሃድ ያሳያል። ከሀገሪቱ እንድወጣ የተወሰደው አስተዳደራዊ ውሳኔ በኢትዮጵያ ላሉት አውሮፓውያን ጥብቅናዬንና ለአውሮፓም የፖለቲካ ጸሐፊነቴን ለማቆም የተወሰደ እርምጃ ነው።

በኢትዮጵያ ለሚገኙና ብቃት ላላቸው ባለሥልጣናት በተለይም ለሠለጠኑት አገሮች ሌጋሲዮኖች በግለሰብ የሚሰራጨውን እውነታ ያለ አንዳች ችግር ማሳወቅ፡ የራሳቸውንም ሆነ በስራቸው ያሉትን ሁሉ መብታቸውን ማስከበር ግዴታቸው ነው። ነገሩ ይበልጥ ጠንክሮና ስር ሰድዶ የአውሮፓ ስልጣኔ ሊያስገኝ የሚችለውን ጠቀሜታ ከማጥፋቱ በፊት አስፈላጊው እርምጃ ሊወሰድ ይገባል።

እስካሁን ድረስ ስለተካሄዱት ሁኔታዎች ለአሜሪካና ለአውሮፓውያን ነጭ ዜጎች ቀላልና የማያሳስብ መስሎ ስለሚታየው ጉዳይ በሚቀጥሉት ገጾች ዝርዝር ማስረጃ ይቀርባል። በተለይም የሃገሬው ሹሞች ስለ ኢትዮጵያ የጻፉት በከፊል ተካትቷል።

## ከኢትዮጵያ ጋር ተያያዥነት ያለው ሥነ-ጽሑፍ

የኢትዮጵያን ችግር ለማወቅ ዋነኛው መሰናከል ተአማኒነት ያለው ዘገባ አለመኖሩ ሲሆን በኢትዮጵያ ውስጥ ስላለው ሁኔታ ካለማወቅና ስለ ኢትዮጵያ የሚጽፉት በግል ግንኙነት ሳቢያ አድሏዊ በመሆን ወይም የንቧን ቀፎ ላለመንካት የወሰኑ በመሆናቸው ነው።

የዘመኑ ተመራማሪ ቡድኖች፡ የተሚላላቸው ጎብኚዎች በፕሮግራማቸው የሚያቀርቡት አገሮችን በበረራ ጉብኝት ማዳረስ በመሆኑ "የተደላደለ ኑሮ" የሚያጣጥሙትና ተገልለው የሚኖሩት የዲፕሎማቲክ ማህበረሰቡ አባላትና የክርስቲያን ሚሲዮናውያን በሀገሪቱ ውስጥ ያለውን እውነተኛ የፖለቲካ ሁኔታ ማወቅ አይቻላቸውም። እውነተኛውና ትክክለኛው ሁኔታ ሊገኝ የሚችለው የሀገሬውን ቋንቋ ከሚያውቁትና ኑሮን ከሀገሬው አኗኗር ከሚካፈሉ ግለሰቦች ብቻ ነው።

ከጥቂቶቹ አጋጣሚዎች አንዱ በቀድሞው ዘመን ከነበረው የመጓጓዣ ችግር (አውሮፕላንና ባቡር) የተነሳ ስለጎበኟቸው አገሮች ለመጻፍ ሲሉ ፈጥነው ሀገሪቱን መልቀቅ ባለመቻላቸው በርካታ ወሮችን እንዲያሳልፉ ይገደዳሉ። ከሀገሬው ሰዎች ጋር በመቆየት ቋንቋውን፣ እውነተኛ አስተሳሰቡንና ባሕሉን ለማወቅ ችለዋል።

የቀድሞ ተመራማሪ ተጓዦች የሀገሬው ሰዎች ስለነጮች ያላቸውን አመለካከት በሚገባ ለመጻፍ ብቃት ያገኙበት መንስኤ ይኸው ነው። ከቀድሞ ሥነ-ጽሑፍ የተወሰደው ተከታዩ ማጣቀሻ ስለኢትዮጵያ የተለየ ባሕርይና ስለአከራካሪው ጉዳይ ያስረዳናል።

"በ1836 ጉዞ በኢትዮጵያ" በሚለው መጽሐፉ (ኮ.ታ. ስቱትጋርት እና ቱቢንገን 1838) ኤ ቮን ካሴ ሲጽፍ "እዚህ ላይ የኔ አመለካከት የኢትዮጵያን ሕዝቦች በተመለከተ ብሩሁን ተሥፋቸውን ለማጨለም የታሰበ መስሎ ቢታይ ያ የኔ ጥፋት አይደለም። ነጮች ይጠላሉም ይፈራሉም ‹ረቂቅ ፍጡራን› ተብለው ቢታሰቡም በዚህ ምክንያት ግን ተወዳጅ አይደሉም። ለአንድ የነጭ ዘር በኢትዮጵያ ስር ተጨቁኖ ከመኖር የከፋ ሁኔታ የለም። እያንዳንዱ

ሰው በበታችነት የመመልከት መብት ያለውና እንዳሻው እንዲያስተናግዱት የተፈቀደለት ይመስላል። በዚህ የተነሳ በሁኔታው ሞራሉ ተሰልቦ ክፉኛ ስለሚጎዳ ወደ አሰቃቂና የዘቀጠ ሰብአዊነት ይወርዳል። ይህ ደግሞ የሰው ልጅ የመጨረሻው ሀብት የሆነውን ሰብአዊ ንብረት ማጣት ነው። ይህን በመሰለ ተሥፋ አስቆራጭና በሚዘገንን ሁኔታ ውስጥ ለረጂም ዓመታት በኢትዮጵያ የሚኖሩ ግሪኮችና አርመናውያን አሉ።

> ከሕገወጥነትና ከጥላቻ በስተቀር ምንም በአላየሁባቸው በእነዚህ ሰዎች ላይ ያደረብኝ ጥላቻ ስር የሰደደ ስለሆነ ለምርምር በተጓዝሁባቸው ስፍራዎችና በአጋጠሙኝ ሁኔታዎች ሁሉ ጨርሶ ልፍቀው አልቻልም። እኔነቴን የተቆጣጠረው የሚያስጠላ ስሜት እየዳበረ ሄዶ የትም አጋጥመውኝ የማያውቁ ወራዳና አስከፊ ሰዎች የሚኖሩበትን ሀገር ጀርባዬን ሰጥቸ ተሰናበትሁት።

እነዚህ ጥቂት ቃላት ለሁለት ሳምንታት በኢትዮጵያ የቆየ ነጭ ታዛቢ ከሚኖረው አስተሳሰብ ጋር ተመሳሳይ ይሆናሉ። ባለፈውም ሆነ አሁን ነጻ አስተሳሰብ ያላቸው ጥቂት የውጭ ሰዎች /ጃፓንንና የአሜሪካን ጥቁሮችን ጨምሮ/ በኢትዮጵያ ምንም ያህል ከርመው በነጻና ከማንም ተጽእኖ በተላቀቀ መንፈስ በኤኮኖሚና በፖለቲካ ባህሪያቸው ኢትዮጵያዊያን ጉዳት ሳያስከትሉባቸው ሃሳባቸውን እንዲገልጹ ቢደረግ ከፍ ብሎ ከተጠቀሰው አመለካከት ውጪ አይሆኑም።

# የኢትዮጵያ መሪዎች ስለሕዝባቸው ያላቸው አመለካከት፤

ስፓነር፣ ሊፐዚግ (1869) “ኢትዮጵያ ከፍታ ላይ ያለች የሀሩር አውራጃ ሀገር” በሚል ርዕስ ባሳተመው ባለ 94 ገጽ ሥራው ላይ ዶ/ር አንድሬ እንደሚከተለው አስነብቧል።

> ወደ ኢትዮጵያውያን ባህርይ መለስ ብለን ስናጤን በብዛት የሚጋጩ ግላዊ አስተያየቶች ያጋጥሙናል። ይሁንና በጥቅሉ ለመናገር እንደ አውሮፓውያን አመለካከት የሚመሰገን አይደለም። ለምሳሌ ሙንዚንገርና ሂውግሊን በዳኝነታቸው ላላ ያሉ ቢሆኑም በብሩስ፣ ሩፔል፣ ክራፕፍ፣ እና አይስበርግ ግን ሁኔታውን አጠንክረው ሲኮንኑ ተደምጠዋል፤ ከሀገሩ ዜጎችም በእርግማኑ የሚሳተፉ በርካታ ሰዎች አሉ።

ስለአገሩ ሰዎች፣ በተለይ ደግሞ ስለዳግማዊ አጤ ቴዎድሮስ የሀገሪቱ ሃይማኖት ከፍተኛ ባለሥልጣን የነበሩት አቡኑ (ሊቀጳጳሱ) በ1843 ለአይስበርግ ሲጽፉ:-

ኢትዮጵያውያን ለዕውቀትም ሆነ ለመማር ምንም ፍቅር የሌላቸው ሲሆኑ፣ የሚከናወነው ማንኛውም መልካም ነገር ለነሱ ጥቅም መሆኑ አይገባቸውም። የሚፈልጉት ነገር ቢኖር ያለህን ንብረት ሁሉ በነጻ መካፈል ብቻ ነው!

**ሩፔልም ሲጽፍ፡-**

የኢትዮጵያውያን ሥነ ምግባርና ባሕርያቸው ስንፍና፣ ስካር፣ ኃላፊነትን መዘንጋት፣ ወራዳነት፣ ሸፍጥ፣ ስርቆት፣ ጣዖት አምልኮ፣ ከንቱ ውዳሴ፣ ራስ ወዳድነት፣ ከፍተኛ አጭበርባሪነት፣ ውለታቢስነት፣ ግድየለሽነት፣ ውለታ ጠያቂነትና መጠን የለሽ ውሸት መለያቸው ነው" ይላል።

**በአፍሪካ ቀዳሚ የሆነው ሣይንሳዊ ተመራማሪ ጀምስ ብሩስ በበኩሉ ስለኢትዮጵያውያን የ"ዓባይ ምንጭ መነሻ ወደ ሆነችው አፍሪካ (ኢትዮጵያ) የተደረገ ጉዞ" በሚለው ጽሑፉ ላይ "በአብዛኛው የለየላቸው ውሸታሞች ናቸው።" ሲል አስፍሯል። ስለኢትዮጵያ የተጻፉትን ሥነ-ጽሑፎች በጥንቃቄ ያነበበው የግብጹ የፍልስፍና ዶክተር በ1928 በጻፈውና "ዩቶጵያ" በተሰኘው የዲግሪ ማሟያ ጽሑፉ ላይ "ኢትዮጵያውያን ለውጭ ዜጎች የአላቸው ሴራ፣ ጥላቻ፣ ውሸትና ሸፍጥ በተደጋጋሚ የሚሰማ ነው" በማለት በማጣቀሻ ገጹ ላይ ያስነብባል።[1]**

**"የንጉሥ ሰሎሞን ዝርያዎች ነን" የሚሉት የኢትዮጵያ መሪዎች ስለሕዝቦቻቸው የሚረዱት የባሕርያቸውን አጉልነት ነው። የዳግማዊ ምኒልክ አያት ንጉሥ ሣህለ ሥላሴ አንድ ወቅት ስለዚህ ጉዳይ አንስተው ለዲፕሎማቱ ሃሪስ ሲናገሩ "የእኔዎቹ ሰዎች መጥፎዎች ናቸው" ማለታቸውን "በሸዋ የተካሄደ አምባሳደራዊ ጉዞና በደቡብ ኢትዮጵያ እረፍት ከ1841-43" በተባለው መጽሐፉ አስነብቧል።**

**ታላቁ ንጉሠ ነገሥት ዳግማዊ ምኒልክ ጥብቅ እርምጃ መውሰድ አስፈላጊ መሆኑን በመገንዘብ በሌቦች ላይ ይወስዱት የነበረውን የእጅ መቁረጥ ቅጣት የውጭ ሰዎች ቢያወግዙትም እሳቸው ስለድርጊቱ ያቀረቡት መልስ ግን "ሰዎቼንና የሚያስፈልጋቸውን የማውቀው እኔ ነኝ" የሚል ነበር። ኢትዮጵያውያን ራሳቸውን የማስተዳደር ብቃት ስለሌላቸው የሌሎችን መብት የማክበር ግዴታ ማስረጽ የሚቻለው ቆራጥ እርምጃ በመውሰድና በመቅጣት ብቻ መሆኑን ምኒልክ በሚገባ ተገንዝበዋል።**

**አንድ ደራሲ የኢትዮጵያውያንን የምሥጢር መጋረጃ ገልጦ ስለከፉ ባሕርያቸው ትክክለኛውን ምስል ቢያስቀምጥ ጸረ ውጭ ዜጎች ስለመሆናቸው አይጠራጠርም። በፈረንሳዊው ደራሲ አርማንድ ላይ** (une desagreable partie de champagne Paris 1931) **ያልተስማማ በሻምፕ አከል ሥራ ላይ እንደተደረገው**

1 ጂ ኬ ሬይንና ትክክለኛ መረጃ ያላቸው የአባዲ ወንድሞች ዘገባ፣ የጀርመን ዲፕሎማቶች ወኪል ዚነግራፍ ፖለቲካዊ ማስታወሻ("በመሞት ላይ ያለው የይሁዳ አንበሳ")እና አርኖልድ ሆልትዝ ("በዋይታው ዋዜማ" (በጂ. ስታይላይክ በ1919 በርሊን የታተመ)፤ ዋይት ዊልዴ በእንግሊዝኛ ስብስብ ሥራው ውስጥ «ዘመናዊት ኢትዮጵያ»፣ በፈረንሳይኛ ታሪካዊ ስራዎች፣ የቦሬሊ ማስታወሻዎች እና የኤም ዴላዝ (ያልታተመ)።

መጽሐፉ ወደ ኢትዮጵያ እንዳይገባ ገደብ ከመደረጉም አልፎ "ማንኛውም ኢትዮጵያዊ ይህን መጽሐፍ ይዞ ቢገኝ አይቀጡ ቅጣት የሚያስቀጣ ወንጀል ነው" ተብሏል።

በመጻሕፍትና በሌሎችም የኅትመት ውጤቶች ደጋፊ ጽሑፎች ስለ ኢትዮጵያ ጥሩ የሚናገሩ ድርሰቶች ሁሉ የንግድ ስራቸውን ለማካሄድ ሲሉ በእጅ መንሻ መልክ በሚጽፉ ሰዎች የተጻፉ፣ አለያም ርካሽ ተወዳጅነትን ለማግኘት፣ ወይም በራሳቸው በኢትዮጵያውያን አነሳሽነት የሚታተሙ ድርሰቶች ናቸው።

በዚህ ሁኔታ የኢ. ኤች ሽረንዜል "ችጋር አልባ ሀገር፣ ጊዜ ያጣች ሀገር" (*Land without Hunger, Land without Time*) የሚለው መጽሐፍ ኢትዮጵያን ለውጭ ዜጎች እንደመንግሥተ ሰማያት በማሳየት ማርና ወይን የሚዘንብባት እንጂ የነጮች ደም መፍሰሻ አለመሆኗን የሚያትትና ማዝናኛነትም ያለው መጽሐፍ ነው። በተመሳሳይም (*L'empire des negres blancs*) "የጥቁር ነጮች ግዛት" የተሰኘው የፈረንሳይኛ መጽሐፍ በፈጠራ ታሪክና በሐሰት የተሞላ ነው። በኢትዮጵያ ስላለው እውነተኛ ሁኔታ ከእውቀት ማነስ የተነሳ የተጻፈው ይህ አይነቱ የሃቅ ሰለባ የሚቀርበው በአውሮፓውያን ዕለታዊ ኅትመቶች ላይ በሚጽፉ የግዢ ጸሐፊዎች ነው። ለምሳሌ የዚህ አይነቱ ጸሐፊ "የጄኔቫ መጽሔት" (*Journal de Geneve*) በተባለው የኅትመት መገናኛ ብዙኃን ላይ (በ1934/35) ከሞቱ በርካታ ዓመታት ያስቆጠሩትን ዳግማዊ ምኒልክን በመሪ ጽሑፉ "የወቅቱ የኢትዮጵያ መሪ" በማለት ጽፏል።

ኢትዮጵያውያን የጠብ አጫሪነት ጠባይ እያላቸውም እንደ አልፍሬድ ቮን ሮት ሮስትሆል ያለ ተወዳጅና ተጓዥ ጸሐፊ "ምኒልክ ከገበሬዎች፣ ከጥቁሮች፣ ከልኡላንና ከወርቅ ቆፋሪዎች ጋር ያላቸው ግላዊ ልምድ" በሚል ሥራው የጀርመን ወዳጅ የሆነው "የኢትዮጵያ መንግሥት" በማለት ሲጽፍ፣ ፖውል ብሮዚዮ ደግሞ መላ አውሮፓውያንን የተሳሳተ አመለካከት ለማስያዝና ኢትዮጵያን እንዲወዱ ለማድረግ በመካከለኛው አውሮፓ በስፋት በሚነበበው ጋዜጣ ላይ "የኢትዮጵያ ሕዝብና መንግሥት ጨርሶ በአውሮፓያን ላይ ጥላቻ የላቸውም" ብሏል።

በዋልተር ሚቴልሆልዘር ድጋፍ የተሠራውና ሆን ተብለው በተዘጋጁ ፎቶግራፎች የተሞላው ፊልምም በአውሮፓ ታላላቅ ከተሞች ብቃት ላላቸው ነጋዴዎችና የሕብረተሰብ አባላት ቀርቦ በመታየት ላይ ነው። ፊልሙ የተሠራበት ዋነኛ ዓላማ በፕሮፓጋንዳ መሣሪያነት ለኢትዮጵያ እንዲያገለግልና ኢትዮጵያውያን ምን ያህል የባሕል እድገት እንዳላቸው አውሮፓውያንን ለማሳመን ነው። እንደ እውነቱ ከሆነ ግን እንዲህ አይነቱ ቅጥፈት በኢትዮጵያ የሚኖሩትን አውሮፓውያን ሁኔታ አላሻሻለም፤ ወይም ለመኖር ያለባቸውን ከባድ ጫና አላቃለለላቸውም።

"*L'Italie et L'Abyssinic*" የሚለውና "ፒ ጂ" በሚል የተፈረመበት ረጂም ጽሁፍ "ለታም" ላይ ታትሞ ሲወጣ አዲስ አበባ በሚኖሩት በሁሉም

የአውሮፓ ዜጎች ላይ የእፎይታ ስሜት አደረባቸው። ፓሪስ የሚገኘው የፈረንሳይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ልሳን ጄኔራል ደ ቦኖ (በዚያን ጊዜ የጣልያን ቅኝ ግዛቶች ሚኒስትር፣ አሁን የኤርትራና የሶማሌላንድ ዋና ኮሚሽነር) "ራሴኛ ኢታልያና" (*Rassegna Italiana*) ላይ ረጂም ዲስኩር አደረገ። ይኸው ጽሑፍ በ"ቴምፕስ"[2] ላይ ለህትመት ሲበቃ "አካፋን አካፋ" በማለት በትክክለኛ ስማቸው በመጥራት የሚከተለውን እውነት ያዘለ መግለጫ ሰጠ።

> ኢትዮጵያ ከጃፓን ጋር በተከታታይ ስላደረገችው ውል፣ የኢትዮጵያ መንግሥት ዝንባሌ አውሮፓውያን በኢትዮጵያ ውስጥ የኢኮኖሚ ይዞታ እንዳይኖራቸው ለማድረግ የተደረገ አካሄድ በመሆኑ አስፈላጊውን እርምጃ በመውሰድ ኢትዮጵያ ደግማ እንድታስብበት ከማድረግ የምንዘገይበት ምክንያት አይኖርም። አስፈላጊ ሆኖ ከተገኘም ጣልያን ከባድ እርምጃ ለመውሰድ ማቀድ አለባት። ይህን ተግባር ጣልያን በራሷ ኃላፊነት የምታካሂደው ሲሆን አስቀድማ ግን ከሁለቱ የ1906ቱ የለንደን ስምምነት (ኮንቬንሽን) ፈራሚዎች ጋር መወያየትና መግባባት አለባት።

"የፖለቲካው ሁኔታ" በማለት ጽሑፉ ሲቀጥል

> ኢትዮጵያ ወደ ዓለም ማኅበር እንድትገባ ድምጽ የቸሯትን አገሮች ሁሉ በመቃወም ላይ ነች። በሀገር ውስጥ ካለው የእርስ በርስ ግጭት፣ በ1932 በተፈጠረው ሁኔታ የልጅ ኢያሱ ደጋፊዎች በሚያሳዩት ቅሬታ፣ በመካሄድ ላይ ያለውን የባሪያ ንግድ በተመለከተ እነዚህ ድጋፋቸውን የሰጡ አገሮች ጣልቃ ለመግባት አልፈለጉም። አሁን ግን የራሳቸውን ጥቅም የሚነካ ሁኔታ በመፈጠሩ የተነሳ ለጥያቄው ዘላቂ መልስ ለማስገኘት ሲሉ ውሳኔ ላይ መድረስ አለባቸው። አስፈላጊ ሆኖ ከተገኘም ኢትዮጵያን በጣልያን ስር ሊያደርጉ ይገባል።

ታህሳስ 11 ቀን 1934 "በርሊነር ሎካላንዚገር" በተባለ ጋዜጣ ላይ "ኢትዮጵያና የአውሮፓ ኃይላት" በተሰኘው መሪ ጽሑፌ ላይ ኢትዮጵያ በዳግማዊ ምኒልክ ዘመን ከነበረችበት ስርዓት ያላት፣ የተባበረች፣ በአግባቡ የምትዳደር ሀገር፣ ለአውሮፓውያንም ምቹና በቀላሉ የምትደረስ ከመሆን ይልቅ የተበጠበጠች፣ በማንኛውም ሁኔታ ደኅንነቷ የተፋለሰ፣ በጥላቻ የተሞላች ሆናለች ብዬ ነበር። የዚች ሀገር መንግሥት ከዓለም አቀፉ ሕብረተሰብ ጋር የገባውን ውልና ስምምነት ሆን ብሎ በዘዴ በማሰናከልና በማፍረስ ሕዝቦቿም ከበላዮቻቸው በሚሰጣቸው ትዕዛዝ በመነሳሳት በውጭ ዜጎች ላይ ጥላቻን ያካሂዳሉ። የጥቁርን ዘር በመላ በኢትዮጵያ አመራር ስር በማድረግ በነጭ ዘር ላይ ያነጣጠረ ውጊያ እንዲያካሂዱ እየጣረች ነው።

[2] ቁጥር 26409 ለ18.12.1933

## ፪

# "ጥቁር መጽሐፍ"

# የኢትዮጵያውያን የጥቃት ስንዘራ

ማንኛውም የውጭ ዜጋ ገና እግሩ የአፍሪካን ምድር እንደረገጠ በእንግድነቱ ተከብሮ አቀባበል አይደረግለትም "በድል አድራጊው የይሁዳ አንበሳ" አገር ነጭ ሰው እንደ ልዩ ፍጡር ነው የሚታየው። ጊዜ እያለፈ ሲሄድም ክብሩ እያሽቆለቆለ ይሄዳል። በኢትዮጵያ የሚኖሩት የውጭ ዜጎች ምንገዜም ቢሆን ከወቀሳ ነጻ ተደርገው አይታዩም። ሌላው ቀርቶ በባቡርም ሆነ በአውቶቡስ ላይ እንኳ ከዜጎች የበለጠ እንዲከፍሉ ይደረጋል። የኢትዮጵያ ታላላቅ ባለሥልጣናት ትዕግስት በሚያሳጣ ባሕርያቸው፣ ከቆሻሻውና ተባይ ከሞላው ልብሳቸው ጋር በአንደኛ ማዕርግ ይስተናገዳሉ።

የውጭ ዜጎች ከሀገሬው ጋር በእኩል ደረጃ መስተናገድን ሊተገብሩት ቀርቶ ሊያስቡት እንኳ አይችሉም። ሁሉም ነገር በአድልዎ ስለሚከናወን የውጭ ዜጎች ዝቅ ተደርገው ነው የሚታዩት። በኢትዮጵያ ሕግ መሠረት የውጭ ዜጋ በሀገሪቱ ውስጥ ቋሚ ንብረት ሊያፈራና የቤት ባለቤት ሊሆን ጨርሶ አይችልም። መብቱ ቤት ተከራይቶ መኖር ስለሆነ ማንኛውም ሁኔታ የሚወሰነው በአከራዩ በጎ ፈቃድ ነው። በቤት ሠራተኛ አስተዳደርም የውጭ ዜጋው በቀጠረው አገልጋዩ ላይ እንደሀገሬው መብት ኖሮት ቅጣት ሊጥልበት አይፈቀድለትም።

ምንም እንኳ የውጭ ዜጎች "ከሁሉም የተሻሉ አገሮች" በሚለው አንቀጽ መሠረት እንደ ዓለም አቀፍ ውል ፈጻሚ አገሮች የጥገኝነትና የነዋሪነት መብት ቢኖራቸውም ከሌጋሲዮኖቻቸውና ከቆንሲላዎቻቸው ሊያገኙ የሚገባቸውን ድጋፍና ጥበቃ ባለማግኘታቸው የተነሳ በኢትዮጵያውያን ዘንድ በዝቀተኛነት ለመታየት ተዳርገዋል።

ይህን በተመለከተ ግልጽ ሊደረግ የሚገባው ጉዳይ የሀገሬው ሰዎች ያላቸው ስሜት የስድብና የማንጓጠጥ ሲሆን በዳግማዊ ምኒልክ ዘመን ግን

እንዲህ አልነበረም። አሁን ግን በመንገድ የሚተላለፍን የውጭ ዜጋ /ወንድም ይሁን ሴት/ ያላንዳች ሰበብ በስድብ ማዋረድ የተለመደና የዕለት ተዕለት ተግባር በመሆን ላይ ነው።

ማንኛውም የውጭ ዜጋ መጀመሪያ የሚሰማቸው የአማርኛ ቃላት "ቆሻሻ" ወይም "የፈረንጅ ቆሻሻ፣ ነጭ ውሻ" የሚሉ ናቸው። በኢትዮጵያውያን መኻል "ነጭ" የሚለው ቃል የተለመደ የማዋረጃ ቃል ነው። ይህ የሆነበት ምክንያት ነጭ ቀለም ከሚያቃጥል የበረሃ ንዳድ ጋር ስለሚመሳሰል የጥላቻ መጠቀሚያ ለማድረግ በመምረጣቸው ነው።

የዚህ ውርጅብኝ መነሻው ከዘራቸው አመጣጥ የሚነሳ የተምታታ አስተሳሰብ ሲሆን "ከግብጽ"ና "ከእስራኤል የመጣን ነን" ብለው ስለሚያምኑና ስለውጭ ዜጎች አለቆቻቸው የሚሰጧቸው መመሪያና ያላቸው ጥላቻ ያስከተለው ውጤት ነው። ከዚያ ባለፈ ነጮች የሚሏቸው የውጭ ሰዎች ለሀገሪቱ ሊሠሩ የመጡ ቢሆኑም የሀገሬው ሰዎች ራሳቸውን ከነጮች በላይ አድርገው ያስቀምጣሉ። ሥራ በኢትዮጵያ ምንግዜም ውርደት ወይም አሳፋሪ ተግባር ሆኖ ይታያል።

የሚከተለው ተረትና እኔም ማስረጃ የምሆንበት የሚያስደንቀውን "የታላላቆቹ ዘሮች" የሚለውን አስተሳሰባቸውን ለማስረዳት ጠቃሚ ይሆናል። አንድ ኢትዮጵያዊ ግራዝማች በአዲስ አበባ ሰማይ አውሮፕላን ሲከንፍ አይተው "እናንተ ነጮች ለመሆኑ በአውሮፓ ከዚህ ጋር የሚወዳደር ነገር አላችሁ?" በማለት ጠይቀዋል።

እያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ የኢትዮጵያ ወታደሮች ከአውሮፓ ቅኝ ገዢ ወታደሮች የበለጡ ለመሆናቸው ከልቡ የሚኮራበት እምነት ሲኖረው፣ የሕዝባቸው መጠን ምን ያህል እንደሆነ፣ የጦራቸው ትጥቅና መጠን ስፋቱ ምን ያህል እንደሆነ ጨርሶ አያወቅም። ከዚህ መደምደሚያ ላይ የደረሰበት ምክንያት በ1896 የተካሄደው የአድዋ ጦርነት ትውስታው ነው።

ለአማራው አስተሳሰብና በኩራት ማበጥ ምክንያት በመሆናቸው የአውሮፓ መሪዎች ተጠያቂዎች ናቸው። ምክንያቱም በመልካም ባሕርይና በተለየ ሰብአዊነታቸው ለዳግማዊ ምኒልክ በተሰጣቸው ከበሬታ በመሞኘት ታላላቆቹ መንግሥታት ምኒልክ ካረፉ በኋላ በቀጣዩ ንጉሥ ሥርዓተ ንግሥ ላይ እንዲገኙ ወኪሎችና ተጠሪዎች እስከመላክ በመድረሳቸው ነው። አውሮፓውያንና ሌሎች የውጭ ኃይላት ያልተገነዘቡት ነገር አሁን ሥልጣኑን የያዙት ንጉሥ ትክክለኛውን ወራሽ በማስወገድ ዘውድ መጫናቸውን አለማወቃቸው ነው። ይህ አለቦታው የተደነቀረ ዲፕሎማሲያዊ ቸርነትና ከበሬታ የኢትዮጵያውያንን ብልግና በእጅጉ አግንኖታል። ሊነሳ የሚገባው አሳፋሪ ጉዳይ ንግሥናውን ለማክበር ሀገራቸውን ወክለው የተገኙት እነዚህ ዲፕሎማቶች ለመኝታ የሚሆን ቦታ እንኳ አልተዘጋጀላቸውም፤ ይህ ደግሞ በትንሹ ሊደረግ የሚገባው ነገር ነበር።

የቀድሞው ልዑል ራስ ተፈሪ መኮንን "ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ንጉሠ ነገሥት" ተብለው ዘውድ ሲጭኑ የኢንግሊዙ ንጉሥ ልጅ የግሎስተሩ ዱክ ማርሻል ፍራንቼት ደ ኤስፔሬ እና ሌሎችም የአውሮፓ አገሮች ልዑላንና

ጄኔራሎች ከሁሉም መደብ ከተሰባሰቡት ጥቁሮች መኻል ለአቧራና ለፀሐይ ቃጠሎ ተጋልጠው ቆመው ዋሉ። ቀጥሎም በአዲስ አበባ መንገዶች ላይ የጀርመኑ ንጉሥ ዊልሃይም ንብረት በነበረው ሠረገላ ንጉሡ በቀድሞው የአውስትሪያ ሃምሳ አለቃ በቼክ ኮቫሊንካ አሽከርካሪነት ሲዘዋወር እንግዶች በአናታቸው ላይ ከሚወርደው የፀሐይ ንዳድ መዳን አልቻሉም ነበር። ቼክ ኮቫሊንካ ለግልጋሎቱ ከፍያ ውል ቢፈርምም ክፍያውን ለማግኘት ረጂም ጊዜ ወስዶበታል። ከንጉሡ የዘውድ በዓል ጋር በተያያዘ ልዩ ልዩ ሥራ እንዲሠሩ በቅጥር የተዋዋሉት አውሮፓውያንም ቢሆኑ ክፍያው እስከዛሬ ድረስ አልተፈጸመላቸውም።

ንጉሣውያን ቤተሰቦች በክብረ በዓሉ ላይ ራሳቸውን የተነጠረ ቅቤ ተቀብተውና የወርቅ ዘውድ ጭነው በክብር አለፉ። ወዳጄ ካውንት ኤች ከተከበሩት እንግዶች መኻል ጫማ አልባ ሆነው በወርቅ ባሸበረቀ ልብሳቸው ደምቀው ሲጓዙ የነበሩ አንድ ባላባት ፎቶግራፍ የማንሳት እድል አጋጠመው። ሰላማዊ በዓሉን ለማወክ ከተንቀሳቀሱ ጥቂት ረባሾች ለመከላከል ክቡርነታቸው ያሸበረቀውን ወርቀ ዘቦ ካባቸውን ብድግ ሲያደርጉ ነበር ፎቶግራፍ ማንሳት የቻለው።

ይህን ለመሰለ የቀልድ ክብረ በዓል ነበር የአውሮፓ ታላላቅ ኃይላት በከፍተኛ ደረጃ ላይ ያሉትን ሹሞቻቸውን የላኩት። ያልሠለጠኑ ሕዝቦች ለአውሮፓውያንና ለተወካዮቻቸው ከበሬታ ሲነሱ ዝም ብሎ መመልከት እንዴት ይቻላቸዋል? ሕጋዊ ንጉሠ ነገሥት መሆኑን አምነው ለማይቀበሉት ሰው ወኪሎቻቸው እንዲሰግዱ መፍቀድ እንዴት ሆነላቸው?

# ተከታታይ ግጭቶች

በማኅበራዊ ጉዳዮችና በባህል ያልሠለጠኑት የአፍሪካ አገሮች ወዴት እያመሩ እንደሆነ ከአራት ዓመታት በፊት በአዲስ አበባ ከተማ በአሜሪካዊው ሚኒስትር ላይ የተፈጸመውና እስካሁንም የሚታወሰው ጥቃት በቂ ማስረጃ ይሆናል። ሚኒስትሩ የአሜሪካን ሰንደቅዓላማ እያውለበለበ መኪናውን ሲያሽከረክር፤ የዓለም አቀፍ ሕግ በሚፈቅድለት መሠረት በነጻ ሊንቀሳቀስ የሚችል መሆኑ እየታወቀ በኢትዮጵያዊ ፖሊስ ተጎትቶ ከወረደ በኋላ ተገረፈ። ከዲፕሎማሲያዊ አድካሚ ውትወታ በኋላ በተፈጸመው ድርጊትና ለአሜሪካ ሰንደቅዓላማ ተገቢው ከበሬታ ባለመደረጉ ይቅርታ ተጠይቆበታል። በአካባቢው ለነበሩት ኢትዮጵያውያን ድርጊቱ “ለነጮች” የሚቸር የእንኳን ደህና መጣችሁ አቀባበል ተደርጎ ተወስዷል።

ስድብና የመብት መደፈር በሌሎችም የዲፕሎማቲክ አባላት ላይ በተደጋጋሚ የታየ ሂደት ነው። የጀርመኑ ሚኒስትር ኤክዝ ዌይስ ሚስት በኢትዮጵያ ፖሊሶችና ሲቪሎች ተደብድባለች[3]፤ ስሟን የሚያጠፋ ጸያፍ

3 እዚህ ላይ የተመለከተው አጋጣሚ የኢትዮጵያን ባለ ሥልጣናት ወግ አጥባቂነት እና በውጭ መንግሥታት ተወካዮች ላይ የሚፈጽሙትን ጋጠወጥነት የሚያሳይ ነው።ሰኔ 18/1935 ምሽት ላይ አንድ የኢትዮጵያ የበረራ መኮንን የጣልያን ሌጋሲዮን ጸሐፊ መኪና በአዲስ አበባ በሚገኝ አንድ የቴአትር ደጃፍ ላይ ቆሞ ሳለ ከመኪናው ላይ የጣልያንን ባንዲራ በቁጣ ነቅሎ ወሰደው።

ስድብም ተሰንዝሮባታል። በቅርቡም የጣልያን ኤምባሲ ፖስታ አመላላሽ ከዓለም አቀፍ ድንጋጌ ውጪ ተይዞ የዲፕሎማቲክ ቦርሳው በግዴታ ተበርብሯል።

ኢትዮጵያውያን በአውሮፓውያን ላይ የሚያደርሱት ጥቃት እየተባባሰ በመሄዱ፣ በርካታ የጀርመን ዜጎች የኅብረት ፊርማቸው የሰፈረበትን ማመልከቻ በበርሊን ለሚገኘውና የዲፕሎማቶች ጉዳይ ኃላፊ ለሆነው የውጭ ጉዳይ ቢሮ ሹም ቻንስለር ጄኔራል ቮን ሽሌይክኸር በአዲስ አበባ የሚገኘው የጀርመን ቆንስላ ለሚደርሰው ጥቃት አስፈላጊውን እርምጃ እንዲወስድ መመርያ እንዲሰጥላቸው ጠይቀዋል። ጥቅምት 10 ቀን1932 በላኩት የድረሱልን ጥያቄ የተፈጸመውን ጥቃት በዝርዝርና በቅደም ተከተል በማስረጃ አስደግፈው በማቅረብ የኢትዮጵያ ፖሊስ ለስርዓት፣ ለሠላምና ለደኅንነት አደገኛ እየሆነ መምጣቱን አስረድተዋል። ቆንሲላዎቹ መብት የማስጠበቅና ስርዓት እንዲሰፍን የማድረግ ዐቅም በማጣታቸው በውጭ ዜጎች ላይ የሚደርሰው ጥቃት እየተባባሰ በመሄድ ላይ ነው።

ለጸጥታ የተመደቡት ፖሊሶችም በነጮች ላይ የሚካሄደውን ጥቃት እያዩ ዝም ብለው ከማለፋቸውም በላይ የነጮች ሚስቶችና ሌሎች ሴቶች ጎዳና ላይ በቆሙ ኢትዮጵያዊያን ሲጎነተሉና ሲሰደቡ አንዳችም ጥበቃ አያደርጉላቸውም። እኔ በበኩሌ አንድ የዓለም አቀፍ ፖሊስ ግብረኃይል ግብጽ ውስጥ እንዲቋቋምና አመራሩን የእንግሊዝ ፖሊሶች እንይዙት እንዲደረግ ሐሳብ አቅርቤያለሁ።

ተቀማጭነቱ በአዲስ አበባ የሆነው ነባሩ የዲፕሎማቲክ ቡድን ወኪል የፈረንሳዩ ክቡር ፓውል ቮርሽሬ ድ ርፌይ በጥር 1933 “በዲፕሎማቲክ አባላት ላይ የሚካሄዱት ተከታታይ ጥቃቶች ትኩረት ተሰጥቷቸው በጥንቃቄ እየታዩና እየተመከረባቸው ነው” የሚል ማስታወሻ አስተላልፏል።

እኔም በተጠቀሰው ማስታወሻ መነሻነት የጥቃቱን ዝርዝር በመተንተን ወቅታዊነቱን ለዲፕሎማቲክ ወኪሉ በጥር 23/1933 አስረድቻለሁ። ለጉዳዩ ከፍተኛ ትኩረት በመስጠትም ለኢትዮጵያዊው የአገር ጉዳይ ሚኒስትር ለደጃዝማች መኮንን የከተማውን ሠላምና ጸጥታ፣ የህዝቡን ስርዓት የለሽነት ያባባሱት ስርዓት አልበኞችና ለተሰማሩበት ኃላፊነት ብቃት የሌላቸው ፖሊሶች መሆናቸውን የሚያስረዳ ደብዳቤ በየካቲት 1934 አስገብቻለሁ። በመጨረሻም በጥር 1935 ለዓለም ማኅበሩ ጸሐፊና ለሚመለከታቸው ሌሎች ባለሥልጣናት፣ እንዲሁም ለአውሮፓውያን ጋዜጦች ያስገባሁት ማስታወሻ በሀገሪቱ በመካሄድ ላይ ያለውን አሳሳቢ ሁኔታ በዝርዝር የሚያስረዳ ነበር።

ከ1932—1934 የተካሄደውን ሁኔታ የሚያስረዳው ክፍል ተመርጦ በዚህ ምዕራፍ ቀርቧዋል። ሆኖም ከተካሄዱት የጭካኔ ድርጊቶች ጥቂቱን በመምረጥ ብቻ የቀረበ ሲሆን አንዳንድ ጉዳዮች ድርጊቱ የተፈጸመባቸውን ሰዎች ስም ለመጠበቅ ሲባል ስማቸው አልተጠቀሰም። የሀገሪቱ መንግሥት ግን ጉዳዩን በአግባቡ እንዲያውቀው ከመደረጉም በላይ ለሚመለከታቸው አገሮችም ዘገባው ደርሷቸዋል።

በግንቦት 29/1932 በዚህ መግለጫ ከተጠቀሱት መኻል በፈረንሳይና ኢትዮጵያ የባቡር ኩባንያ የሚሠሩ በርካታ ፈረንሳዮች ሚስቶቻቸውና ልጆቻቸው በአንድነት በድሬዳዋ ከተማ ማዘጋጃ ቤት ፖሊስ አባላት በአስከፊ ሁኔታ ጥቃት ደርሶባቸዋል፣ ተደብድበዋል፣ ተንሳቁለዋል። በከተማው በሚኖሩ የውጭ ዜጎች ላይ በተካሄደ ሰላማዊ ሰልፍ ጥቃት ሲሰነዘር አንዳንዶቹ ወደ መኖሪያ ቤታቸው በመግባት ከጥቃቱ ለመዳን ቢሞክሩም አልተሳካላቸውም። በዚህ ሳቢያ የፈረንሳዩ ሚኒስትር ድ ርፌይ ድሬዳዋ በግንባር በመገኘት የመረረ ቅሬታውን በማሰማቱና የምድር ባቡር ሠራተኞች ከግንቦት 30 እስከ ሰኔ 3 ድረስ የሥራ ማቆም አድማ በማድረጋቸው የኢትዮጵያ መንግሥት በመጠኑም ቢሆን የማስተካከያ እርምጃ ለመውሰድ ተገዷል።

በ1932 በጋ ወቅት የጀርመኑ ተወላጅ ኤፍ ኤች እና ጂ ዩ ቤታቸው አጠገብ በሀገሪቱ ዜጎች ከታገቱ በኋላ የጀርመን ሌጋሲዮን ጣልቃ በመግባቱ ነጻ ሊሆኑ ችለዋል። በወቅቱ ደግሞ የቆንሲላዎችን መብት የሚያስጠብቀውንና ደኅንነታቸውን የሚያረጋግጠውን ልዩ የቆንሲላዎች መብት በመጣስ ኢትዮጵያዊው ዳኛ በታጠቁ ዘበኞቹ ታጅቦ ወደ ጀርመኑ ኤም ኤል ፒ ግቢ ገብቶ ጥቃት አደረሰበት።

በነሐሴ 20/1932 በኢጣልያ ቆንሲል ጥበቃ ስር የነበረውና "ቢ ኤች" የተባለው ሁንጋሪያዊ ሞጆ ከተማ ላይ በአጥቢያ ሹሙ በገብረ ጊዮርጊስ በተሰጠ ትእዛዝ መሠረት እየተጎተተ ከአጥቢያ ሹሙ ፊት ቀርቧል። የባለሥልጣኑ ታዛዦችም "አንተ ቆሻሻ ጣልያን" እያሉ ከመስደብ አልፈው በጠብመንጃቸው ሰደፍ ደበደቡት። በአጣና ገርፈው፣ ጭንቅላቱን ዘቅዝቀው በባቡር ሐዲድ ላይ ጎተቱት። በመጨረሻም በባቡር ጣቢያው አዘዥ አረብ ዕርዳታ ከባሰ መከራ ሊገላገል ችሏል። አዲስ አበባ ካለው የኢጣልያ ሌጋሲዮን ጋር የሚያገናኘው የስልክ መስመርም ተበላሽቶ ነበር። ድርጊቱን የፈጸሙት ሰዎች ማንነት በግልፅ ቢታወቅም የኢትዮጵያ መንግሥት እስካሁን ድረስ በአጥፊዎቹ ላይ አንዳችም ማስተካከያ አላደረገም፤ ለቆንስላውም ስለ ጉዳዩ ማብራሪያ አልተሰጠም።

በጥቅምት 14/1932 ምሽት የቼኮስላቫኪያው ጋዜጠኛ አዲስ አበባ በሚገኘው ራስ መኮንን ድልድይ ላይ በሀገሬው ሰዎች ተይዞ በዱላ ክፉኛ ቆስሏል። በዚህ ጊዜ ከድርጊቱ አራት ሜትር ርቀት ላይ ቆሞ የነበረው የጥበቃ አባል ለተጎጂው ዕርዳታ በማድረግ ፋንታ ተመልካች ሆኖ ነበር። ለምን ዕርዳታ እንዳላደረገ ሲጠየቅ "ለገበያ ወጥቶ የነበረ አንድ መሶብ እንጀራ በመጠበቅ ላይ ስለነበርሁ ነው" አለ። ጥፋተኞችን ለማደን ማዘዣ እንዲያወጣ ልዩ ችሎቱ ቢጠየቅም "የድርጊቱን ፈጻሚ ስም ካላመጣችሁ" በሚል ጥፋተኞቹ ሳይያዙና ሳይቀጡ ቀርተዋል። ከአቴንስ የተላከው ጥያቄም አንዳች ውጤት አላስገኘም።

በጥቅምት 1932 አርመናዊው ኤች በራስ መኮንን ጎዳና ከሚኖርበት ቤት በፖሊስ ተገዶ ከወጣ በኋላ በዛቻና ማስፈራራት መከራውን አይቶ በስንት ተማጽኖ ከግርፋት ድኗል። ማስገደዱን በተመለከተ ከፈረንሳይ ቆንሲል ለቀረበው ጥያቄ ከፖሊስ ምንም መልስ አልተሰጠም።

በታሕሳስ 7/1932 የማቅለሚያ ሠራተኛው ኢ ኤች ኤፍ ጉለሌ መንገድ ላይ በሃያ የፖሊስ አባላት ጥቃት ተፈጽሞበታል። በዚህ ጊዜ ጀርመናዊው ኢ ኤ (የፈረንሳይና ኢትዮጵያ የንግድ ኩባንያ ሥራ አስኪያጅ) በጠመንጃ ሰደፍ ተደብድቦ ክፉኛ ቆሰለ። ይህንንም በተመለከተ ድርጊቱን የፈጸሙት የፖሊስ አባላት ለጥያቄ እንኳ እንዲቀርቡ አልተደረገም።

በታሕሳስ 11 እና 18/1932 ስለቼኮስላቫኪያ ጉዳይ ተወካይ የሆነው ረዳት ባለ ስልጣን ሲ ኤል ኬ እና አጎቱ ጄ ኬ ቅዱስ ጊዮርጊስ ቢራ ፋብሪካ አጠገብ በሀገሬው ሰዎች በድንጋይ ሲወገሩ አንድም የፖሊስ አባል ለዕርዳታ አልደረሰላቸውም።አቤቱታ ቢቀርብም የተገኘው ምላሽ "አቤቱታው የቀረበለት ሰው የሌላ አካባቢ ተመዳቢ በመሆኑ ጉዳዩን መከታተል አልተቻለም" የሚል ነበር።

በተመሳሳይ በታሕሳስ 18/1932 ወደ ምሽት አካባቢ የቤልጂግ ምክትል ቆንስላ ባለበት ጥቂት የቤልጂግ ተወላጆችና ቤተሰቦቻቸው በማርቨኮስ ምግብ ቤት በተቀመጡበት ዘመናዊ ልብስ በለበሱ ወጣቶችና በሌሎች ኢትዮጵያውያን ከምግብ ቤቱ እንዲወጡ ዘለፋና ግልምጫ ሲሰነዘርባቸውና ሲባረሩ ፖሊስ በአካባቢው ነበር። ሴቶቹ /የውጭ ዜጎች/ "ሸርሙጦች" እየተባሉ ከመሰደባቸውም በላይ "በኢትዮጵያ ያሉት ነጭ ዜጎች በአጠቃላይ ይገደላሉ" የሚል ማስጠንቀቂያም ያሰሙ ነበር።

በተመሳሳይ ወር አንድ ጣልያናዊ ፍርድ ማከማቻ ጣቢያ በኢትዮጵያውያን ክፉኛ ተደብድቦ ሲቆስል ፖሊስ አንዳችም ዕርዳታ አላደረገለትም። በዚሁ ሰሞን አንድ እድሜው የገፋ የግሪክ ተወላጅ ክፉኛ ተደብድቦ መንቀሳቀስ አቅቶት ሲወድቅና የድረሱልኝ ጥሪ ሲያሰማ ፖሊስ ዕርዳታ ሳያደርግለት ቀርቷል።

የሚቀጥለው አጋጣሚ የኢትዮጵያን ፖሊሶች ባሕርይ በሚገባ ያስረዳል። በ1932 ማብቂያ ላይ የጥበቃ ሠራተኞች ወደ አንድ አርመናዊ ግቢ በጉልበት ገቡ። ባለቤቱ በውጭ ዜጋ ግቢ ውስጥ ምንም ጉዳይ እንደሌላቸውና ድርጊቱ ሕገወጥ መሆኑን ሲያስረዳቸው ምላሻቸው በትዕቢትና በግድየለሽነት የተሞላና "ድሮ አዎን፤ አሁን ግን ሁሉም ነገር ተለውጧል!" የሚል ነበር።

የአዲስ አበባ ፖሊስ አባላት ከሠለጠነውና ሕግን አክብሮ ከሚያስከብረው የአውሮፓ ፖሊስ ጋር በእኩል ደረጃ ሊመደቡ አይችሉም። ይህም በአቋማቸው፣ በተጨማደደ አለባበሳቸውና በአጠቃላይ ሁኔታቸው የተረጋገጠ ነው። ጉቦኝነታቸውን ቃል አይገልጠውም፤ ልመናቸውና ያም ካልተሳካ አስፈራርተው ገንዘብ መቀበላቸው የተለመደ ነው። እንግዳ የሆነ የውጭ ዜጋ ባጋጠማቸው ቁጥር፤ በተለይም በምሽት "ቀረጥ እንቀንስላችኋለን" በማለት የሚያደርሱባቸው መከራ ለመናገር የሚያስቸግር ነው።

በታህሳስ 1932 "የኢትዮጵያ መልእክተኛ" (courier d'Ethiopie) ላይ የወጣው ጽሑፍ አረመኔነት እስከየት ድረስ ሊዘልቅ እንደሚችል ያስገነዝባል። "ዘበኞቹና..." በሚል ለስለስ ያለ ርዕስ የቀረበው ይህ ጽሑፍ አንድ ኢትዮጵያዊ ፖሊስ ከሕጉ በተጻራሪ ለማስለቀቂያ ገንዘብ ማግኛ ሲል የውጪ ዜጎችን የቤት

ሠራተኛ ብቻ ሳይሆን ከቤት ውጭ የታሠረና ንብረትነቱ የአንድ አውሮፓዊ ልጅ የሆነ ፈረስ ጭምር መያዙን ያትታል።

ጥር 2/1933 በአዲስ አበባ የመሳፈሪያ ጣቢያ በሚገኝና በርካታ ሰዎች በነበሩበት አንድ መድረክ ላይ ከአንድ ፈረንሳዊ ዜጋ ጋር በተፈጠረ አለመግባባት በፈረስ ላይ ሆኖ ጥበቃ ሲያካሂድ በነበረ አንድ ፖሊስ ፊቱ ላይ በጅራፍ ተገረፈ።

በየካቲት 12/1933 ፖስታ ቤት አጠገብ በድንገት በተጀመረ እሰጥ አገባ "ኢ.ኤ.ጂ" የተባለ ዳቦ ጋጋሪ በጉራጌዎች ክፉኛ ተጎድቶ በአካባቢው ወደ ነበረ የጀርመን ቤት በመግባት ሕይወቱን አተረፈ።

የካቲት 26/1933 አርመናዊው ፎቶግራፍ አንሺና እርጉዝ ባለቤቱ "ማጄስቲክ ሆቴል" ካለው መኖሪያ ቤታቸው ባጠገብ እንደቆሙ በተወረወረባቸው ድንጋይ ከፍተኛ ጉዳት ሲደርባቸው በጥቂት ርቀት ላይ ቆሞ ድርጊቱን ይመለከት የነበረው ፖሊስ ያደረገላቸው ከለላ የለም።

በግንቦት 1933 መጨረሻ ላይ ታክሲ ነጂው የአርመኑ ተወላጅ ለአንድ ባለሥልጣንና አገልጋያቸው ለሰጠው የማጓጓዝ አገልግሎት ሂሳብ በመጠየቁ የተነሳ በከፍያው ፈንታ ለግርፊያ ተዳርጎ ጉዳት ደርሶበታል፤ የታክሲው መስታወትም ተሰባብሯል።

በ1933 የበጋው ወቅት መጀመሪያ ላይ በአርሲ ክልል የጀርመኑ ገበሬ ኢ. የ16 ዓመት ሴት ልጅ በአንድ የኢትዮጵያ ባለስልጣን ተጠልፋ በራሱ በባለሥልጣኑ ቤት ታገተች። የንጉሡ ልጅ ባል ራስ ደስታ ዳምጠው በዚያ ያልፉ ስለነበር ጉዳዩ ተነገራቸውና በእሳቸው ጣልቃ መግባት ታጋቿ ተለቀቀች።

በግንቦት 1933 መጨረሻ ላይ የቀድሞው ራሽያዊ ጄኔራል ዲ ባልቴት ባለቤት "አጠፋሽ" ተብላ በአዲስ አበባ ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን አደባባይ መሬት ለመሬት እየተጎተተች በዘበኞች ተደብድባለች።

በሐምሌ 1933 የጀርመን መንግሥት ጥበቃ ያለው ቼኮዝሎቫኪያዊው የቡና ገበሬ ጄ ኤፍ አንድ የሀገሬው ተወላጅ ከብቶች በማሳው ላይ ጥፋት አደረሱበት፤ በዚህ የተነሳ በሐሰት ክስ ተመስርቶበት ከራሱ ግቢ ተገዶ እንዲወጣ ከመደረጉም በላይ በወረዳው ዳኛ በቀኛዝማች ጎሽሜ በተሰጠ ትእዛዝ 60 በሚሆኑ አጃቢዎች በሰደፍ ተመትቶ ወደቀ። ሆዱ ላይ በተደጋጋሚ በመረገጡ በርካታ ስሮቹ ለጉዳት ተዳርገዋል። ሕጻን ልጁም ለዱላ ተዳርጋለች። ይህ ሁሉ ሲፈጸም ኢትዮጵያዊው ባለሥልጣን በመዘባበት "አውሮፓውያን ሌቦች ናችሁ" በማለት ይሳደብ ነበር። ዱላው የቆመው ተደብዳቢው አቅም አጥቶ መንቀሳቀስ ሲሳነውና ራሱን ሲስት ነው። በፈረንሳይ ሌጋሲዮን አማካኝነት ጉዳዩ ለአዲስ አበባው ልዩ ፍርድ ቤት ቢቀርብም፤ የቼኮዝሎቫኪያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የላከው የፍትሕ መጠየቂያ ደብዳቤ አንዳች ውጤት አላስገኘም፤ የሴትዮዋ ጉዳት ለዕድሜ ልክ ቁስለት ቢዳርጋትም ትኩረት የሰጣት አካል አልነበረም።

በጥቅምት 1933 በተከበረ የሰብል ምርት ክብረ በዓል ላይ ተካፋይ የነበሩ ጥቁር አሜሪካውያንም የኢትዮጵያውያንን ጭካኔ ቀምሰውታል። ከተሳታፊዎቹ አንደኛው ለማስፈራራት ሲል ሽጉጡን ሲያወጣ ተረባርበው በመያዝ ክፉኛ ጎዱት፤ ወደ ሆስፒታል ተወስዶ ነፍሱ ቢተርፍም አንድ እግሩ ግን በዚሁ ሰበብ ተቆርጧል።

በ1933 መኸር ወቅት አንድ አሜሪካዊ ሚሲዮናዊና ባለቤቱ በሀገሬው ዜጎች ንብረታቸው ሁሉ ተዘርፎ በሸሚዞቻቸው ብቻ ቀርተዋል። የአሜሪካ ሌጋሲዮን ተቃውሞውን ለንጉሠ አቀረበ። ንጉሠ ነገሥቱ ለዚህ የሰጡት ምላሽ "በአሜሪካ አንድ ጥቁር ተመሳሳይ ጥቃት ቢደርስበትና ንብረቱን ቢዘረፍ ምን ታደርጋላችሁ?" የሚል ነበር። ዋሽንግተን ስለ ጉዳዩ ምክር ሲጠየቅ የተሰጠው ምላሽም "ጉዳዩን ችላ በማለት ማለፉ ይመረጣል" የሚል ነበር።

በአዲስ አበባ ያሉት የውጭ ዲፕሎማቶች ያላቸውን ዲፕሎማቲክ ከለላ በመተማመናቸው፣ በስራቸው ያሉትን ዜጎች ችላ በማለታቸው፣ ከኢትዮጵያ መንግሥት ተወዳጅነትን ለማትረፍና በግል ምክንያታቸው የተነሳ አንድነት በማጣታቸው የሃገሬው ሰዎች በአውሮፓውያንና በሌሎች የውጭ ዜጎች ላይ የሚያደርሱት ጥቃትና ሕገ ወጥ ተግባር ከቀን ወደ ቀን እየከፋ በመሄድ ላይ ነው። ቆንስላዎቹና ሌጋሲዮኖች ለሚፈጸመው ሕገወጥ ተግባር ያላቸው ድክመትና ግድ የለሽነት የሀገሬው ሰዎች ያሻቸውን ለማድረግ እንዲችሉ ይገፋፉቸዋል።

በጥቅምት 8/1933 አዲስ አበባ በሚገኘው የነጻነት አደባባይ ላይ በበርካታ ነጮችና በአዲስ አበባ ፖሊስ መኻል የተፈጸመው አጋጣሚ[4] ከፍ ብዬ በጠቀስሁት የቆንስላዎችና የሌጋሲዮኖች ድክመት ሳቢያ የመጣ መሆኑን ያረጋግጣል። ከምዕራቡ ክፍለ ሀገር የመጡት ጥቁሮች በስዊዙ የሙዚቃ መሪ የተዘጋጀውን የሙዚቃ ትርኢት የሚያቀርቡበት ቀን ነበር። ይመጣሉ ተብሎ ከተወሰነበት ሰዓት 15 ደቂቃ ቀድመው በቦታው ሲደርሱ የአካባቢውን ስርዓት ለማስጠበቅ የተሰማሩት ፖሊሶች በወሰዱት እርምጃ ከሕዝቡ ጋር ብጥብጥ ውስጥ ገቡ። የቤልጅግ አሰልጣኞችና አዛዦች ወደ ትርኢቱ ቦታ ገና በመምጣት ላይ ነበሩ።

በትርኢቱ ቦታ የነበሩት ፖሊሶች ያለምንም ልዩነት ሕዝቡን መግፋት ጀመሩ። ቀደም ብሎ ግን የውጭ ዜጎች ከሐውልቱ ቀጥሎ ባለው ቀለም በተመለከተበት ቦታ ላይ፣ የሀገሪቱ ዜጎች ደግሞ ባሻገር ባለው ስፍራ ላይ እንዲቆሙ ተወስኗል። በተፈጠረው ግርግርና ግፊያ የውጭ ዜጎች ከተመደበላቸው ክልል አልፈው ወደ ሀገሬው ሰዎች ተጠጉ፤ ሊመለሱ ቢሞክሩም በተፈጠረው ረብሻ ምክንያት አልሆነላቸውም።

በሁኔታው የተደናገጡት ዘበኞች በያዙት ጅራፍ ነጮቹን በጅምላ በመግረፍ፣ ሴቶቹን በማመናጨቅና በጉልበት በመጠቀም ገፈተሯቸው። ቁጥር 208 የሆነው ፖሊስ አንዷን ነጭ ጡቷን በመያዝ ከሕዝቡ ወደኋላ አሽቀነጠራት። "ጂ ዩ" የተባለው ጀርመናዊ በድርጊቱ በመናደድ ዘበኛው ላይ

4 በ13.10.1933 "የኮንሰርቱ ፖሊስ" በሚል ርዕስ በ"ኩርየር ደ ኢትዮጲ" ላይ ታትሞ የወጣ።

ተከመርበት። ይህን ያዩት ወደ 10 የሚጠጉ ፖሊሶች ጀርመናዊውን ተረባርበው በመጣል ባርኔጣውን፣ አለንጋውንና ገንዘቡን ዘረፉት። ቤልጂጋውያኑ የፖሊስ አባላትና አሠልጣኞች በስፍራው በመድረሳቸው ጀርመናዊውና ሌሎች ነጮች ለባሰ አደጋ ከመጋለጥ ሊድኑ ቻሉ።

በጥቅምት 10/1933 "ኢ ፒ" የተባለው የጀርመን ሞተር ጠጋኝ "የትራፊክ ደንብ ጥሰሃል" ተብሎ በኢትዮጵያዊ ፖሊስ /ቁጥር 123/ ከመንገድ ላይ በግዳጅ ተያዘ። በሀገሩ ልማድ መሠረት ትራፊክ ፖሊሱ ድንጋይ አንስቶ በመወርወርና በስድብ ከማዋረዱም ባሻገር እጁና ራሱ ላይ አቆሰለው። በዚህ የወንጀል ድርጊቱ እንዲጠየቅ አቤቱታ ቢቀርብበትም የፖሊስ ባለሥልጣናት የተለያየ ሰብብ በመፍጠርና "ተከሳሹ የማየት ችግር አለበት" በሚል ሰንካላ ሰበብ ከክሱ ነጻ አደረጉት።

አሁን ደግሞ በጥቅምት 1933 መጨረሻ ላይ አዲስ አበባ በሚገኘው "ታባሪያስ" ቡና ቤት ስለተፈጸመው ሕገ ወጥ ድርጊት፣ በውጭ ዜጎችና በዜጎቹ መኻል ስላለው አሳሳቢ ውጥረት ላነሳ ነው። በጥቅምት 22 አስር የሚሆኑ የአውሮፓ ልብስ የለበሱና ከመጠን በላይ የጠጡ ወጣት ኢትዮጵያዊያን ወደ ቡና ቤቱ በመግባት በዚያ በነበሩት ነጮች ላይ ዘለፋና ማንጓጠጥ እያደረጉ ሰላም መንሳት ጀመሩ። ፈረንሳዊው የቡና ቤቱ ሥራ አስኪያጅ አካባቢውን ለቅቀው እንዲወጡ ሲያደርግ "መሣሪያችንን ይዘን መጥተን እዚህ ያሉት ነጫጭ ሴቶች አብረውን እንዲደንሱ እናደርጋለን" በማለት ዝተው ሄዱ። የሀገሪቱ ባለሥልጣኖች እነሱ ስለሆኑ በሚመለሱበት ጊዜ ተቃውሞ ቢገጥማቸው መሣሪያቸውን ሥራ ላይ እንደሚያውሉት አስጠነቀቁ። አንድ ነጭ ቢገደል የሚያስከተለው ነገር አይኖርም፤ ይኸው ድርጊት በአውሮፓውያን ላይ በየቀኑ የሚፈጸም ስለሆነ ሌጋሲዮኖቹ ሊያደርጉ የሚችሉት ምንም ነገር አልነበረም።

እሑድ ጥቅምት 29/1933 ጠዋት በጊዮርጊስ ኅሩይ /የኢትዮጵያ መንግሥት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ልጅ/ መኖሪያ ቤት ውስጥ የኢትዮጵያውያን ወጣቶች ስብሰባ ነበርና የሚከተለው ታቀደ። አንድ ቡድን ከ"ታባሪስ" ሆቴል ፊት ለፊት በሚገኘው በማጀስቲክ ሁቴል አዳራሽ ተዘጋጅቶ እንዲጠብቅ ሆኖ ሌላው ቡድን ሽጉጥና ረጃጂም ስለት የታጠቁ አባላትን ይዞ ታርጋው በተሸፈነ ግራጫ መኪና ተጭኖ ወጣ። በርካታ ጠመንጃ የታጠቁ አሽከሮች ደግሞ ከቡና ቤቱ አጠገብ በሚገኝ ሰዋራ መንገድ ላይ "በተጠባባቂነት" ተመደቡ። ልዩ መታወቂያና ፈቃድ ሳይኖራቸው የሀገር ልብስ የለበሱ ኢትዮጵያውያን ከመሸ በኋላ በመንገድ መተላለፍ ስለማይፈቀድላቸው ከፍተኛ ጥንቃቄ አድርገዋል።

ወደ አራት ሰዓት ገደማ የወጣት ኢትዮጵያውያን ሁኔታ አስጊና አደገኛ እየሆነ ሲሄድበት የቡና ቤቱ ሥራ አስኪያጅ /የኮርሲካው ተወላጅ/ ሕጋዊ መብቱን በመጠቀም "ውጡልኝ" አለ። የፖሊስ አባላትና የማዘጋጃ ቤቱ ባለሥልጣናት ጉዳዩ ተነግሯቸው ዕርዳታ ከተጠየቁ በኋላ አንድ ሰዓት ቆይተው መጡ። ፖሊስ ወጣቶቹን ሁለት ጊዜ ከአካባቢው ገለል ማድረግ ችሏል። እንደ ዲፕሎማቲክ አባላት ተጠሪነቱ የፈረንሳይ ኤምባሲ እንዲያውቀው ሳይደረግ ቡና ቤቱ ታሽጎ በታጠቁ አባላት ሲጠበቅ ቆየ። ወጣት ኢትዮጵያውያንም

በዚያ ሂደት ድል ማድረጋቸውን በከተማው በማስተጋባት የከተማውን ነዋሪዎች በነጮች ላይ ማነሳሳት ያዙ። የሀገሬው ዜጎችም ጸጥታ በማደፍረሳቸው፣ በነጮች ላይ ማነሳሳት ያዙ። የሀገሬው ዜጎችም ጸጥታ በማደፍረሳቸው፣ ግለሰቦችን ሰላም በመንሳታቸውና የግለሰቦችን ነጻነት በመድፈራቸው አንዳችም ቅጣት ሳይፈጸምባቸው ታለፉ። የቡና ቤቱ ባለቤትም ሀገሪቱን በአስቸኳይ ለቆ እንዲወጣ ተገደደ። ንብረቱም ያለበትን እዳ መሸፈኛ ሆኖ ሲከበር በአዲስ አበባ ኗሪ የሆኑ ነጮች ለስድብና ለማስፈራራት ተዳረጉ።

# አውሮፓውያንን ለጉዳት የሚዳርገውና የማይለወጠው አያያዝ፤

በኢትዮጵያ ያለውን የዳኝነት ደረጃ በሁለት መመደብ ተገቢ ነው። በነጮች ላይ ጥቃት የሚሰነዝሩ የሀገሬው ሰዎች ሳይቀጡ ይታለፋሉ፤ አብዛኛዎቹም ይሰወራሉ። በሌላ ደንብ ደግሞ አንድ የውጭ ዜጋ የቀጠራቸውን አገልጋዮቹን ትዕግስትና ማስጠንቀቂያ ሳይመልሳቸው ቀርቶ ሕግ በሚፈቅድለት መሠረት አካላዊ ቅጣት ቢፈጽምባቸው ወዲያውኑ ለፍትሕ ይቀርባል።

ለምሳሌ ጀርመናዊት ሚስት የነበረችው ግብጻዊው ሐኪም ዶ/ር አይ ቢ ለዚህ ጥሩ ምሳሌ ነው፤ ሐኪሙ ለቅጣት የተዳረገው ወዳጁ የሆኑ ቤተሰቦች ልጃቸውን በህክምና ሙያ እንዲያሰለጥንላቸው በአደራ ሰጥተውት ሳለ ልጁ በተደጋጋሚ ሲሰርቅ ይዞት ከጥፋቱ ለማረም በግርፋት ቀጣው። በዚህ ምክንያት ፍርድ ቤት ቀርቦ የተጣለበትን ውሳኔ "አልቀበልም፤ ቅጣቱ አግባብ አይደለም" በማለቱ በአስቸኳይ ከሀገር እንዲወጣ ተፈረደበት።

አንድ አውሮፓዊ ጋላቢ ወይም ነጮች የተሳፈሩበት አውቶሞቢል አንድን ኢትዮጵያዊ መግደል ቀርቶ ገፋ እንኳ ቢያደርግ በጣም አስፈሪና አደገኛ ሁኔታ ይፈጠራል። በርካታ ሰዎች ይሰበሰቡና በውጭ ዜጎች ላይ ውግዘት ያወርዱባቸዋል። ፈረሱም ሆነ መኪናው በባለቤቶቹና ንቀት በተሞሉት ዘበኞች ወዲያውኑ ይወረሳል። ንብረቱን ማስመለስ የሚችለው ከሕግ ውጪ በሆነና በማያውቀው ተመን ገንዘብ በመክፈል ነው። ተገጪው በበኩሉ መሬት ላይ ተንጋሎ "ሞትሁ፣ ገደሉኝ እኮ" በማለት ይንደፋደፋል። ወዲያው በሽክም ችሎት ሲቀርብ አውሮፓዊው ላይ ከደረሰው ጉዳት ጋር ጨርሶ የማይመጣጠን ከፍተኛ ቅጣት ይጣልበታል። ለዚህ ማስረጃ የሚሆነው በጀርመናዊው ነጋዴ ኤች ደብልዩ ቢ ላይ የተላለፈው የ500 ታህለር መቀጮ ነው።

በሌላም በኩል በድንጋይና በብረት ላይ ቀራጺ የነበረውና አሁን ወደ ግብርና የዞረው ኬ ኤል በአዲስ አበባ ጎዳና ላይ ጠርዙን ይዞ ሲጓዝ መብራትም ታርጋም የሌለውና ችሎታ በሌለው ሰካራም አሽከርካሪ በሚነዳ መኪና ማጀስቲክ ሆቴል አጠገብ ቢገጭም ወንጀለኛውን ለፍርድ ለማቅረብ ወራት ፈጀ። ወንጀለኛው ችሎት ቢቀርብም እስከ ዛሬ ውሳኔ አልተሰጠበትም።

በህዳር 23/1933 የሀገሬው ዜጎች "በአንድ አውሮፓዊ ነዋሪ ዛቻና ማስፈራሪያ ተሰንዝሮብናል" ብለው በማመልከታቸው ፖሊሶች በአውሮፓውያን

ላይ የቤት ለቤት ምርመራ አካሄዱ። ሊደረግ የሚገባው ግን የውጭ ሰዎች በመሆናቸው ጉዳዩ ለቆንስላዎች ሊተው በተገባው ነበር። ቆንስላዎቹም መብታቸውን አሳልፈው ለመስጠት ጊዜ አልወሰደባቸውም። ይሁንና አንዳንድ ጊዜ የቆንስላው የበላይ፣ ሌላ ጊዜ ደግሞ ምክትሎቻቸው የብርበራው አካል በመሆን በታዛቢነት ይገኙ ነበር። ኢትዮጵያውያንም ባላቸው አሳፋሪ ደንብ መሠረት በባዶ እግራቸው ባሉ ጥቁር ፖሊሶቻቸው አማካይነት የነጮቹን ቤትና የሴቶቹን መኝታ ቤት ሳይቀር ይበረብራሉ።

እኔም እንደ ፋሺስት ሀገር አባል ሆኜ በመታየቴና በሀገሪቱ ውስጥ ያሉትን አውሮፓውያን ለአመጽ "ዋነኛ ቀስቃሽና ሽብርተኛ" ተብዬ በመጠርጠሬ በሀገሬው ፖሊሶች ብርበራ ሳይደረግብኝ አልታለፍሁም።

በታህሳስ 6/1933 ጀርመናውያን የቁምሳጥን አናጢዎች ጂ ኤስ እና ኤፍ ኤች ጉለሌ ያለው መኖሪያቸው ለተንኮልና ለአመጽ በተሰባሰቡ የታጠቁ ኢትዮጵያውያን ተከበበ። ወዲያው በሚወረውሩት የድንጋይ ናዳ ንብረታቸው በሙሉ ተሰባበረ። ድንጋዩ በግቢው ተከመረ፤ ሁለት አውሮፓውያን ለቁስለት ተዳረጉ፤ ንብረታቸውም ወደመ። ይህ ሁሉ ሲፈጸም ፖሊስ የደረሰው በጣም ዘግይቶ ነበር። ፖሊሶች የአመጹን አስተባባሪና መሪ ቢይዙትም ወደ ዋናው የከተማው ፖሊስ ቢሮ በሚወሰድበት ጊዜ ቁጥሩ 983 የሆነው የፖሊስ አባል እንዲያመልጥ አደረገው። ስለጠፋው ንብረትና ስለደረሰው ጉዳት ጉዳዩ ለችሎት ቀርቦ እልባት እንዲያገኝ መንግሥት ትዕዛዝ ቢሰጥም "አንድ ጊዜ ዳኛው በሕመም ላይ ነው" በማለት፣ በሌላ ጊዜ ደግሞ (መቼም በዓላቸው ማለቂያ የለውም) በበዓል ሳቢያ፤ በመጨረሻው ቀጠሮም በዝናቡ ወራት ሰበብ ተደርጎ ፍርዱ ተጓተተ።

በ1933 መጨረሻ ላይ በኢትዮጵያ የሥራ ሚኒስቴር ውስጥ ተቀጥራ የምትሰራው የፖላንዷ ኤ ከልጇ ጋር የራስ መከንንን ጎዳና በማቋረጥ ላይ ሳለች በሁለት ኢትዮጵያውያን የእጅ ቦርሳዋን ተዘረፈች። ባጠገቧ የነበሩት ዘበኞች እንዲይዙላት ብትማጸንም በቸልታ አለፉት። በተመሳሳይ ሁለት አርመናዊያን ነጋዴዎች በዚሁ ቦታ በጠራራ ፀሐይ በተሰነዘረባቸው ግፊያ ሳቢያ የገንዘብ ቦርሳቸውን ሲነጠቁ ከዘበኞች አንዳችም ዕርዳታ አላገኙም።

በጥር 15/1934 በአዲስ አበባ ቀዳማዊ ኃይለስላሴ አደባባይ በሚገኘው ኮከብ ቡና ቤት አዘውትረው የሚገለገሉ አውሮፓውያን ላይ በጥንቃቄ በተዘጋጀ ዕቅድ ትንኮሳ ተደረገባቸው። በቡና ቤቱ መግቢያ ላይ አንድ የታወቀ ሐበሻ ቆሞ አውሮፓውያኑ ሲገቡ በአማርኛ "አሳሞች" በማለት የስድብ ሰላምታ እየሰጠ ያስገባቸዋል። አውሮፓውያኑም ከዝምታ ውጪ ምንም አላሉም። ከጥቂት ቆይታ በኋላ ዋናው የትንኮሳው አስተባበሪ በላይኛው ፎቅ ወዳለው ክፍል በመግባት፣ ከጠረጴዛ ጠረጴዛ በመዘዋወር ስድብና ማንጓጠጥ ሰነዘረ። በቡና ቤቱ ባለቤት አካባቢውን ለቆ እንዲወጣ ሲነገረው ግድግዳው ላይ ያለውን የቢሊያርዶ ዱላ በማውረድ ሽማግሌውን የቡና ቤት ባለቤት ቀጠቀጠው። በአካባቢው የነበሩት አውሮፓውያን ሽማግሌውን ለማዳን ሲሞክሩ ተደብቀው

ይጠብቁ የነበሩ በርካታ ኢትዮጵያውያን ከተሸሸጉበት በመውጣት በስፍራው ደረሱ። ወዲያው ግጭት ተነሳና እንደተለመደው ነጮቹ የበላይ ሆኑ።

የድንጋይ ናዳ ከውጭ በመስኮት እየጎረፈ በርካታ ኢትዮጵያውያን በመሰባሰብ አውሮፓውያኑን ሲያስፈራሩ፣ መስኮቶቹ በድንጋይ እሩምታ ሲሰባበሩ መስታወቱ ያወጣው የነበረው ድምጽ እየተሰማ አንድም ፖሊስ ያለመድረሱ የሚያመላክተው ጉዳዩ ሆን ተብሎ የታቀደና አውሮፓውያኑ መሣሪያቸውን ጥቅም ላይ እንዲያውሉ ለማነሳሳትና ጸቡን በማባባስ በአውሮፓውያኑ ላይ የበለጠ ጉዳት ለማድረስ የተሸረበ ሴራ መሆኑን ነው።

ይህ የተለመደ የኢትዮጵያውያን ደባ፣ ይህ ተደጋጋሚ ትንኮሳና ግፌት አውሮፓዊያኑን ካሉበት ትዕግስት አውጥቶ ኢትዮጵያውያን ባለሥልጣናት አለያም መንግሥት የሚወስዱትን እርምጃ "ሕጋዊ" ለማድረግ የሚያስችል ሁኔታ ለማመቻቸት ነው። ከአውሮፓውያን ጋር ከሊዝና ከፈቃድ ጋር በተገናኘ ብዙ ጊዜ የተለመደ አካሄድ አለ። የማይካ ማዕድን ውልን በተመለከተ ከውለታ ፈጻሚው ኤ ቢ ኤስ ጋር ለዓመታት በመካሄድ ላይ ያለው ግጭት የዚህ ማስረጃ ነው። ውለታው ከኤስ ጋር በተፈጸመበት ጊዜ ያሁኑ ንጉሥ እንደራሴ ልዑል ነበሩ። ውለታው ከተፈጸመ 263 ቀናት ቢያልፉም ሥራው የሚከናወንበትን ስፍራ አስመልክቶ እስካሁን ድረስ የኢትዮጵያ መንግሥት የሰጠው መመሪያ የለም።

ቁፋሮውን ለማከናወን የሚያስፈልገውን ድማሚት ወደ ሀገር ማስገባት የሚያስችል ፈቃድ ለማውጣት ወራት ተቆጥረዋል። ያም ሆኖ ታክሱንና ለተመደቡት ተቆጣጣሪዎች ክፍያ መክፈል የተጀመረ ቢሆንም ተቆጣጣሪዎቹ ግን ሥራ ስላልተጀመረ በሥራው ቦታ ላይ አልተገኙም፤ ክፍያው ግን ቀጥሏል። የንብረት ጥያቄ ፊርማ የተሰባሰበበት አቤቱታ በግሪኮች ቢቀርብም ውጤት አላስገኘም። ኤስ ከፈራሚው አካል መፍትሔ ቢጠይቅም ከንጉሡ የተገኘ መልስ የለም።

የተገባው ውል ሳይፈጸም በመቅረቱ ክስ መመሥረት አይቻልም። በውሉ ሰነድ "የኮብሊውስኪ ስምምነት" አንቀጽ 11 መሠረት ውል ተቀባዩና ውል ሰጪው ማለትም የውጭ ዜጎችና በንጉሡ በሚተዳደሩ ሕዝቦች ("Sujets de l'Empereur") መኻል የሚነሳ አለመግባባት በጥምር ልዩ ፍርድ ቤት ውሳኔ መሠረት መፍትሔ ያገኛል ይላል።

ስለዚህ አውሮፓዊ ሸሪክ ወይም በኮንትራት ውል ተባባሪ የሆነ ሁሉ ማንኛውንም በግልግል የሚፈታ አለመግባባት መሠረታዊ በሆነ መመሪያ መገላገልን የኢትዮጵያ መንግሥት ስለማይቀበል "መብቴን የሚያስከብርልኝ ውሳኔ ይሰጠኛል" ብሎ ሊያምን አይችልም።

ከኢትዮጵያ መንግሥት ጋር የተገባ ማንኛውም ውል ወደ ሽምግልና የሚያደርስ ቢሆን ሽምግልናው በታላቅ ብልሃትና ዓላማን ለማሳካት ተግቶ በመሥራት ሊሆን የግድ ነው። ለምሳሌ በኢትዮጵያ በስተምስራቅ በሚገኝ ክፍለ ሀገር ሆስፒታል ውስጥ ይሠራ የነበረው የጀርመኑ የሕክምና ባለሙያ

ዶ/ር ኦ ስዴን በማዕከላዊ መንግሥት ሊከፈለው የሚገባው ደመወዝ እስከዚህ ዕለት ድረስ ሳይከፈለው ነበር የሚሠራው። ስለዚህ ጉዳይ በጀርመን ሌጋሲዮን በሚካሄደው የሽምግልና ግልግል ላይ ጸረ ኢትዮጵያ አቋሚ ስለሚታወቅ ውክልናዬ ተቀባይነት እንደማይኖረው ተወሰነ። ይህ ደግሞ በውሉ ላይ የሰፈረውን የሽምግልና ግልግል አስመልክቶ የሰፈረውን አንቀጽ የሚቃረን ነው።

በአጠቃላይ ኢትዮጵያውያን በተለያየ ሰበብ አውሮፓዊያንን ለመበዝበዝ፣ ደመወዛቸውን ለመቀማት፣ ወይም እስኪሰለቻቸው ድረስ በማበሳጨት ትዕግስታቸው አልቆ ለክስ የሚያደርስ ተግባር እንዲፈጽሙና ኢትዮጵያውያኑ ከሰሰው ውል ማፍረስ እንዲችሉ ለማድረግ ነው። ቀደም ብሎ እንደተገለጸው ኢትዮጵያውያን "የሃገሪቱ ብቸኛ ባለቤቶችና ባለሥልጣኖች ነን" ብለው ስለሚያስቡ በፈለጉት መንገድ ማንኛውንም ጉዳይ ያከናውናሉ።

ሌላ ምሳሌ ለማቅረብ የንጉሡ ንብረት የሆኑትን ፈረሶች ጫማ የሠራበትንና የገጠመበትን ክፍያ የጠየቀው ጀርመናዊው የብረታ ብረት ሥራ ባለሙያ ፒ ፎ ክፍያውን አለማግኘቱና በፍርድ ቤት ባለሥልጣናት ሁሉ ችላ መባሉ ብቻ ሳይሆን፤ ሥራው ካለቀ በኋላ ብዙ ጉልበት፣ ገንዘብና ሙያ ያፈሰሰበትን ንብረቱን ክፍያ ባለመፈጸሙ "አላስረክብም ብሏል" በሚል መንግሥት ቅጣት ጥሎበታል። እንደ አውሮፓዊነቱ ጠበቃ ሳይኖረው ብቻውን ለፍርድ ተጋልጧል። ሕጋዊ የመንግሥቱ ተወካዮች በነጮች ላይ ችግር በሚፈጥር ሁኔታና ሐቁን በመካድ እንደሚሠሩ ያለአንዳች ሐፍረት ይናገራሉ። በ1933 መጨረሻ ላይ አውስትሪያዊው መሐንዲስ ኤች ኤፍ ከሥራ ሚኒስትር ጋር ባለው ስምምነት ለዓመታት ከሠራ በኋላ ክፍያው ባለመሰጠቱ በከፈተው ክስ ቢፈረድለትም የሚኒስትሩ መ/ቤት ወኪል "ፍርድ ቤቱ ቢወስንብንም አንከፍልም" ብሏል።

ችሎቱ ለአውሮፓዊው ቢወስንለትም ከዚያን ዕለት ጀምሮ እንደ ከፍተኛ ጠላት ስለሚታይና ሕይወቱ ለአደጋ በመጋለጡ ኑሮው በፍርሐትና በስጋት የተሞላ ሆነ።

በአውሮፓ ጋዜጦች ሁሉ አስተያየትና ትችት የተሰነዘረበት የኢትዮጵያ መንግሥት ለጉዳዩ ቁብ አልሰጠውም፤ ሐኪሙ ሕይወቱን ለማትረፍ ሲል ሀገር ጥሎ የመጥፋቱ ጉዳይ እስካሁንም ከአብዛኛዎቹ ሕሊና ውስጥ የሚዘነጋ አይደለም። በ1933 በአንዲት ነጭ ሴት ላይ የተቃጣው የመግደል ሙከራ ብዙም አይታወቅም። ስሎቫኪያዊትዋ የቀድሞ የሙዚቃ ባለሙያ የንጉሡ የምግብ ኃላፊ ሆና ነበር። ከስርዓት ውጪ በሆነ መንገድ ስለሚመለከቷትና "ባሪያ" እያሉ ስለሚጠሯት፣ ባልደረቦቿ ባሉበት ስለመቷትና ስለአዋረዷት አቤቱታ በማሰማቷና ከመኳንንቶቹ ጋር በተደጋጋሚ ስለምትጋጭ፤ በደል ያደረሰባትን አንድ ሾፌርም ባደረገው ድፍረት ከሥራ እንዲባረር ስላደረገች የሀገሬው ሰዎች ጥላቻቸው በረታ። በዚህ መሠረት በሀገሩ የሚታወቀውን መርዝ በድብቅ አስገብተው ምግቧ ውስጥ ደባለቁ። በአጋጣሚ መርዙ ቀስ እያለ የሚሰራጭ ኖሮ አንድ አስተናጋጅ በድንገት ምስጢሩን አወጣውና በአጣዳፊ ወደ ፈረንሳይ ሆስፒታል ተወስዳ ለስድስት ሳምንታት በመታከም ከሞት

ተረፈች። ምንም እንኳ ወደሥራዋ መመለስ ባትችልም የሠራችበትን ደምወዟን ማግኘቷም መታደል ነው።

ኢትዮጵያውያን አውሮፓውያንን ምን ያህል እንደሚያሰቃዩዋቸው ለማወቅ አንድ ሰው ለጥቂት ጊዜም ቢሆን በሀገሪቱ መሥራት ይገባዋል። በቤተመንግሥት የሚሠራም ቢሆን ጥቃቱ አይቀርለትም። ለዓመታት የንጉሡ ግቢ የኤሌክትሪክ መሐንዲስ የሆነው ቼኮስሎቫኪያዊው ጄ ዲ ከሁለቱ ታላላቅ ልጆቹ ጋር የወታደር ሰልፈኞች በሚያልፉበት መንገድ ሲያልፍ በአካባቢው ባሉ ሰዎች ተደብድቦ ወደቀ።

አድካሚና አሰልቺ ልምድ የታየበት አጋጣሚ ደግሞ በሁንጋሪያዊው ሐኪም ዶ/ር ኬ ኤም ላይ የደረሰው ጉዳይ ነው። በተሰጠው ውክልና መሠረት ከራስ ኃይሉ ጋር ተፈራርሞ ሳለ ውሉ ወደ ኢትዮጵያ መንግሥት የጦር ሚኒስቴር የደረሰው መብቱን በሚነጥቅ መልኩ ነው።

ጎጃም ውስጥ የመኖሪያም ይሁን ለሥራው የሚሆን ቦታ በአግባቡ ሳይዘጋጅለት ጣራው በከፊል በተበሳሳ ቆርቆሮ የተሸፈነ፣ የከብት ጋጣ የሚመስል ሽታው የማያስጠጋና ከጥርኝ ወጥመድ አጠገብ ያለ ባዶ ክፍል ነበር ለስራው የተሰጠው። ደመወዙ አልተከፈለውም። በተለያየ ወቅት በሚከበር በዓል ላይ በሚከሰት አደጋ የተነሳ የሚቆስሉትን ከፍተኛ ባለሥልጣናት ለማከም ይገደድ ነበር። ውሉ ላይ ቢጠቀስም ከአዲስ አበባ ወደ ጎጃም የተጓጓዘበትን ወጪውን እንኳ አልከፈሉትም። ራሱን ከከፋ ጥቃት ለማዳን ሲል ዶክተር ኤም ከብቶቹን፣ መሳርያዎቹን እና መገልገያ ቁሳቁሶቹን በመላ ባሉበት ትቶ ወደ አዲስ አበባ ተመለሰ። የኢትዮጵያውያን ሕግ “ራሶች አንዳችም ክፍያ አይጠየቁም” ስለሚል የይገባኛል ጥያቄ አላነሳም።

ምንም እንኳ ዶ/ር ኤም በ1930ው የኦሮሞ ሁከት ጊዜ ከፍተኛ ተጋድሎ የፈጸመና የኢትዮጵያ ባለኮከብ የጀግና ሜዳይ ተሸላሚ ነበር። በቀጣዮቹ 1931/1932 ዓመታት ለተካሄደው ወታደራዊ ተልእኮ በጦር ሚኒስቴር ውስጥ በሕክምና ባገለገለበት ወቅት የታየው ግን ስጦታው ወይም ሽልማቱ ምንም ያህል ታላቅ ቢሆን ማንኛውም ነጭ ከኢትዮጵያውያን መቀበል እንደሌለበት በማስጠንቀቂያነት የሚያገለግል ነው።

ዶ/ር ኤም የሚደረግለት መስተንግዶ ደረጃውን የጠበቀና ለአውሮፓውያን በሚመጥን መልኩ እንደሚሆን ተገልጾለት ነበር። ይሁንና በጠቅላይ አዛዡ በገብረማርያም ትእዛዝ መሠረት ያለምንም ስንቅ ነበር ከግንባር ቀደሙ ክፍል ጋር የዘመተው። ጠቅላላ ጓዙ ወደ ኋላ በመቅረቱ ዶ/ር ኤም ያለምንም ምግብና ልብስ ለሳምንታት በበረሃ መጓዝ ተገዶ ነበር። በመጨረሻም ሕይወቱን ለማዳን ወደ ኢጣልያ ሶማልያ ላንድ ተሸገረ። “በእንቅርት ላይ ጆሮ ደግፍ” እንዲሉ ያጠራቀመውን 500 የብር ታህለር ግራዝማች በዛብህ ስለሺ ለጋዳም ገበያ ላይ ዘረፉት።

አዲስ አበባ ከተመለሰ ከወራት ድካምና ሙግት በኋላ ነበር ተራፊ ንብረቱን ለማስመለስ የበቃው። አብዛኛው የፎቶግራፍ መሣሪያዎች፣ የቀዶ ጥገና መገልገያውና ሌሎችም የሥራው ቁሳቁሶች እጋዴን ላይ ከአያያዝ ጉድለት የተነሳ ከጥቅም ውጪ ሆነዋል። ስለተበላሹት ንብረቶቹ ያቀረበውን አቤቱታ ኢትዮጵያውያን ባላቸው የተለመደ የማንቱቻ ዘዴ በመጠቀም ለወራት አዘገዩት። ጉዳዩን የያዙት ከንቲባው ያሁኑ የሀገር ውስጥ ጉዳይ ሚኒስትር ደጃዝማች መኮንን ከ30 ጊዜ በላይ በቀጠሮ አመላለሱት። ከሳሹ ባለበት ውሳኔ እንዲሰጡ ከንጉሠ ነገሥቱ ሶስት ጊዜ ቢታዘዙም ተጋባራዊ አላደረጉትም።

ከፍ ብለው የተጠቀሱት ግራዝማች በዛብህ ስለሺ በጣም የሚያስገርሙ ሰው ናቸው። በታላላቅ ቦታዎች የሚመረጡና የተከበሩ ናቸው። በጣም ውስብስብ የሆኑ ጉዳዮች ሁሉ በምሥጢር የሚሰጡት ለሳቸው ነው። በዶ/ር ኤም ንብረት ላይ በለጋዳሞ ስለተፈጸመው ጥፋት ክስ መመሥረት ያልተቻለው በዚሁ ምክንያት ነው።

በነገራችን ላይ ኢትዮጵያውያን በዚያን ጊዜ በኦጋዴን ያካሄዱት ዘመቻ የኢጣልያ ሶማሌ ላንድን ለማጥቃት ያደረጉት መለኛ እንቅስቃሴ ነበር። በተከታዮቹ 1932/33 ግራዝማች በዛብህ ስለሺ አዲስ አበባ በሚገኘው የንጉሡ እማች ቤት ውስጥ ከእስራኤላዊው የመሣሪያ ደላላ ካቴዝንጎልድ እና ከቤልጂየሙ ቤንዛህል ጋር ድርድር ላይ ነበሩ። እርግጥ ይህ ድርድር በጦር ሚኒስትሩ በኩል በይፋ የታገደ ነበር።

የኢትዮጵያ ወታደራዊ መኮንኖችና ከፍተኛ ሹማምንት የጦር መሣሪያዎችንና ሌሎችንም አስፈላጊ የጦር እቃዎች በድብቅ ከሚነግዱ ሰዎች ጋር ነው የሚገበያዩት። ግዢው የሚፈጸመው ለኢትዮጵያ ሠራዊት ቢሆንም በግላቸውና ለግላቸው በማስመሰል በአካባቢው ያሉ ቅኝ ገዢዎች ሳያውቁት በአካባቢው ሹማምንትና የጎሳ መሪዎች በመታገዝ ነበር ግዥውን የሚያከናውኑት። ግዢው ከተከናወነ በኋላ በኮንትሮባንድ የተገዛው መሣሪያ በድብቅና በምሽት አሰብ ላይ ይራገፋል፤ ከዚያም በግመል ተጭኖ አዲስ አበባ ይደርሳል።[5]

ይህ ስውር የኢትዮጵያውያን የትጥቅ ዝግጅት እና በሌሎች ግዛቶች ላይ የጦር ወታደሮችን ዝግጁ አድርጎ መጠበቅ በአውሮፓውያን ላይ ለሚፈጸመው የጥላቻ ድርጊት ትክክለኛ ማመሳከሪያ ነው።

---

5 በዚህ በኩል መሣሪያዎችን በሕገ ወጥ መንገድ (በኮንትሮባንድ) ማስገባት በመከልከሉ አሁን ማዘዋወር የሚቻለው በእንግሊዝ ቅኝ ግዛቶችና በሱዳን በኩል ነው፤ የመሣሪያና መሰል የጦር መገልገያዎች ቁጥጥር የሚደረገው በኢትዮጵያ፣ በጣልያን፣ በፈረንሳይ እና በእንግሊዝ መካከል ነሐሴ 29/1930 በተፈረመው ስምምነት መሠረት ሲሆን፣ የቁጥጥር ኃላፊዎች ደግሞ ሶስቱ ታላላቅ አገሮች ናቸው። በመጀመሪያው (1935) ግማሽ ዓመት ኢትዮጵያ የሚያስፈልጋትን ታስገባ የነበረው በጅቡቲ ድንበር ሲሆን 16,000 ጠበንጃዎች፣ 600 አውቶማቲክ መሣሪያዎች፣ የቼኮስሎቫኪያ ሥሪቶች የሆኑ ጥይቶችና ስዊዘርላንድ ሠራሽ የሆኑ ሁለት ጸረ አውሮፕላን መሣሪያዎች ነበሩ። 1400 ጠመንጃዎች፣ 2850 ካርባይን ጠመንጃዎች፣ 7,000,000 ጥይቶች፣ በዘጠኝ ሳጥን የታሸጉና 900 ፓውንድ (408.2328 ኪሎግራም) የሚመዝኑ ጀርመን ሠራሽ ኬሚካሎች እና ሁለት ሳጥን የጋዝ መርዝ ወደ ሀገር ለማስገባት ፈቃድ ተጠይቆ ነበር።

# በውጭ አገር ዜጎች ላይ የሚፈጸመው የኢትዮጵያውያን ጥቃት

የወቅቱ ዓለም አቀፋዊ ተጨማሪ በሽታ በመሆን ላይ ነው። በአጎራባች የቅኝ ገገሮች፣ በታላቋ እንግሊዝ፣ በፈረንሳይ፣ እና ጣልያን ይዞታዎች ላይ በታጠቁና በተደራጁ የኢትዮጵያ ሠራዊት አባላት ተከታታይ ጥቃትና ወረራ ተካሂዷል።

ቀደም ብሎ የተጠቀሰው ወረራ በኦጋዴን እስከተካሄደበት እስከ 1932 ድረስ የኢትዮጵያ ወታደሮች የእንግሊዙን የወረዳ ኮሚሽነር አጃቢዎች አርቺሳ ላይ፣ ሌሎች የእንግሊዝ ዜጎችን ደግሞ በፓስቶራሂ የእንግሊዝ ሶማሌ ድንበር ላይ ገደሉ።

በጥር 16/1933 የሃውሳው ሡልጣን ኢትዮጵያን በደቡብ ምዕራብ ከፈረንሳይ ሶማሊያ ጋር የሚያዋስነውን የፈረንሳይ ቅኝ ግዛት አካል ከ5000 ባላነሱ ወታደሮች በመውረር በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ስም የዲኪል ምሽግ እንዲሰጥ ጠየቁ።

በጥቅምት 1933 መጀመሪያ ላይ ኢትዮጵያውያን አኝዋኮች የእንግሊዝ ቅኝ ግዛት በሆነችው ሱዳን ላይ ወረራ በማካሄድ በርካታ መንደሮችን አቃጠሉ፤ ብዙ ቁጥር ያላቸውን ሱዳናውያን ገድለው 73 ሴቶችንና ሕጻናትን ከበርካታ መንጋዎች ጋር ዘረፉ። ለዚህ ሁሉ በደል የእንግሊዝ መንግሥት ሊያገኝ የቻለው ምላሽ 67 ሴቶቹንና አነስተኛ የካሣ ክፍያ ነው።

በጥቅምት 1934 አጋማሽ ምሽት ላይ የታጠቁ የኢትዮጵያ ወታደሮች በደንብ በታቀደ ጥቃት ጎንደር በሚገኘው በጣልያን ቆንሲላ አካባቢ በሚገኝ ንብረት ላይ ጉዳት አደረሱ። ጥቃቱ የተደመደመውም ከጣልያን ወገን አንድ ሰው ሞቶ ሁለት ከቆሰለ በኋላ ነው። በጣልያን መንግሥት በቀረበው የተቃውሞ አቤቱታ የጎንደሩ ገዢ ይቅርታ ጠየቀ፤ የፖሊስ አዛዡም ከምድብ ሥራው ሲነሳ የኢትዮጵያ የጦር ክፍል አባላት ባርኔጣቸውን አውልቀው በጣልያን ሰንደቅ ዓላማ ፊት የክብር ሰላምታ አቀረቡ። ጥቃቱን ጠንስሰዋል የተባሉትና በቁጥጥር ስር ውለው የነበሩት ሰዎችም ከጥቂት ጊዜ በኋላ በኢትዮጵያ መንግሥት እንዲለቀቁ መደረጉ የኢትዮጵያውያንን ትክክለኛ ጠባይ የሚያሳይ ነው።

በጥቅምት 23/1934 የእንግሊዝና ኢትዮጵያ የድንበር ኮሚሽን አባላት ከከተማ ውጪ ወዳለ የጣልያን ጦር ሠፈር ሲቃረቡ የታጠቁትን የኮሚሽኑን አጃቢዎች የኢትዮጵያ ወታደሮች ወደ ጣልያን ሶማሊያ ድንበር ማለፍ ከለከሏቸው። በዚህ ጊዜ ኢትዮጵያውያን ወታደሮች በአቅራቢያቸው ካለው ገርሎጉቢ ሠፈራቸው ድጋፍ ሰጪ ኃይል በማስመጣት በጥቅምት 5 በአዛዣቸው በጄኔራል ፊታውራሪ ዓለማየሁ መመሪያ መሠረት በጣልያኖች ላይ ጥቃት ከፈቱ። በወልወሉ ተከታታይ ግጭት በጣልያን ላይ የደረሰው አደጋ ከባድ ነበር፤ 40 ሞቱ፤ 400 ቆሰሉ።

በወልወል አጋጣሚ ሰር ጆን ሲሞን ጥቅምት 17/1934 ለምክር ቤት ባቀረበው አይነት በኢትዮጵያና በሶማሌላንድ መሀል ያለው ድንበር አከላለል በግልጽ አልተቀመጠም። ስለዚህ ጉዳይ በኢትዮጵያ መንግሥት የተሰጠው ማስረጃና በርሊን ባለው የኢትዮጵያ ቆንሲል ጄኔራል በጥቅምት 1934 የወጣው መግለጫ እርስ በርሱ የሚቃረን በመሆኑ ተቀባይነት የለውም። መግለጫው በአንድ ወገን "ግጭቱ የተከሰተው በወሠን ኮሚሽኑ ሥራ ነው" ሲል በሌላ በኩል ደግሞ "ሁኔታው የተካሄደው በኢትዮጵያ ወሠን ውስጥ ነው" መባሉ የማይጣጣሙ ሰበቦቹ ናቸው።

በጥር 21/1935 በኢትዮጵያ ጠረፍ ያሉ የደናኪል ጎሳዎች በአብሄ ሐይቅ የሚገኘውን የፈረንሳይ ሶማሌ አጠቁ። በዚህም 88 የሶማሌ ዜጎች ገደሉ። ግጭቱ ቀጥሎ አስተዳዳሪና የግንባሩ አዛዥ ሚስተር በርናርዲንና በጂቡቲ የተመደቡትን የቅኝ ገዢው ኃይል ተዋጊ የሆኑ 18 የሴኔጋል ወታደሮች ተገደሉ። እንደተለመደውም የኢትዮጵያ መንግሥት ኃላፊነቱን በሙሉ አልተቀበለም። የፈረንሳይ ሪፑብሊክ መንግሥት ትንሽም ቢሆን ዋስትና ሊያገኝ የቻለው አጠቃላይ ሁኔታው የኢትዮጵያ መንግሥት ኃላፊነት ሆኖ በመገኘቱ ነው። የኢትዮጵያ መንግሥት ለጉዳዩ የሰጠው ምላሽ የዚህ አይነቱ ሁኔታ እንዳይደገም ለመወያየትና ስርዓት ለማስያዝ ፈቃደኛነቱን መግለጹ ብቻ ነው። ሕይወታቸው ላላፈው 107 ሰዎች ይኸ ምን ዓይነት ማካካሻ ነው? እንዴትስ የተሳካ ውጤት ሊሆን ይችላል?

ጥር 29/1935 የኢትዮጵያ ወታደሮች እንደገና በአፍዱብ አካባቢ የሚገኘውን የጣልያን የጥበቃ ጣቢያ አጠቁ። አዲሱ የኢትዮጵያውያን ወረራ የጣልያን ቅኝ ግዛት በሆነችው በሶማሌ ላንድ ላይ እየተባባሰ በመሄዱ ጉዳዩ አሳሳቢ ስለሆነና ወደ ሌሎች አጎራባች ሥፍራዎችም ሊስፋፋ ስለሚችል የኢጣሊያኖች ትዕግስት ፈተና ላይ ወደቀ፤ በዚህ የተነሳ በርካታ የጦር ኃይል በማጓጓዝ ለመልሱ መዘጋጀት ያዙ።

የካቲት 20/1935 የታጠቁ የኢትዮጵያ ወታደሮች በኤልቢርና በአጋቤ በኩል የጣልያን ሶማሌን በድንገት ወረሩ። በዚህም የጣልያንን ካማሪዴሪ (ወታደሮች) በማስበርገግ 100 ግመሎችን ሰርቀው ወደ ኢትዮጵያ ድንበር ተመለሱ። በተፈጸመው ስርቆት በዓየር ክትትል ሊደረግበት ከተሞከረ በኋላ ሊያስከትል የሚችለውን አለመግባባትና አላስፈላጊ ውዝግብ ለማርገብ በማሰብ ክትትሉ ተቋረጠ።

በዚሁ ወር 23ኛው ቀን ምሽት በአንድ ዝቅተኛ መኮንን በሚመራ ወታደራዊ ቡድን ላይ ወደ ጣልያን ክልል 300 ሜትር አልፈው በገቡ የኢትዮጵያ ወታደሮች ተኩስ ተከፈተበት። አንድ የጣልያን ወታደርም ከባድ የመቁሰል አደጋ ደረሰበት። በአዲስ አበባ የሚገኘው የጣልያን ተወካይ ወረራውን በተመለከተ ድርጊቱ የዓለም አቀፉን ውልና ሕግጋት የጣሰ መሆኑን በማስረዳት ለደረሰው ጉዳት የኢትዮጵያ መንግሥት ካሣ እንዲከፍል ጠየቀ።

ሚያዚያ 10/1935 እንደገና በጣልያን ቡድን ላይ ጥቃት ተሰንዝሮ ዘረፋ ተካሄደበት። ይህም ኢትዮጵያውያን ጥቃታቸውን በእቅድ እንደሚያካሂዱ የሚያሳይ ሆነ። በተመሳሳይ ወቅት የአገሬው ሰዎች ለቀጣይ ወረራ በመነሳሳት በፋፍና በፎካ ወንዝ መኻል በሸፍ ማሩዲን ግዛት ሥር ያሉትን ኢትዮጵያውያን ጥቃት ሰነዘሩባቸው።

ግንቦት 4/1935 ሁለት አጋጣሚዎች ተፈጠሩ። አንዱ በኤርትራ፣ ሌላው ደግሞ በጣልያን ሶማሌ። በደናኪል ግዛት በሚገኘው የጣልያን የጥበቃ ጣቢያ ላይ ኢትዮጵያውያን ጥቃት ሰንዝረው 30 የጣልያን ወገን የሆኑ ተወላጆችን በመግደል 2000 የቀንድ ከብቶችን ዘረፉ። በዚህ ጊዜ በዋቢ ሸበሌ አሳራባች ሙስታሂል ላይ 20 የሚሆኑ የታጠቁ ኢትዮጵያውያን የጣልያንን ክልል በማለፍ የተሰጣቸውን ማስጠንቀቂያ ችል በማለት ተኩስ ከፈቱ።

በ1935 ሰኔ ወር መግቢያ ወሠን በማስከበር ተግባር ላይ በነበሩ መደበኛ የሱዳን ወታደሮች ላይ የታጠቁ ኢትዮጵያዊያን ተኩስ ከፈቱ። ካይሮ የሚታተመው "ሙስዋር" የተባለው ጋዜጣ ጥቃቱን በተመለከተ ባቀረበው ሐተታ ጥቃቱን የፈጸሙት የኢትዮጵያ ወታደሮች ወደመጡበት ሊመለሱ የቻሉት በመትረየስና በቦምብ በታገዘ የእንግሊዝ ዓየር ኃይል አማካይነት ነው።

ሰኔ 6/1935 ወደ ድሬዳዋ በመኪና ይጓዝ የነበረው የሐረሩ የጣልያን ቆንሲላ አባል መንገድ ላይ ከፈረሰኞች የጦር ቡድን ጋር ተገናኘ። የኢትዮጵያ ወታደሮች ማስፈራራትና የከፋ ስድብ ካደረሱበት በኋላ ሊይዙት ተጋበዙ።

በዚያው ቀን በሐረር የሚገኘው የጣልያን ቆንሲላ አባል የሆነው ካቫስ ወደ ምድብ ሥራው በመሄድ ላይ እያለ ሃያ የሚሆኑ ኢትዮጵያዊያን ወታደሮች፣ የከተማው ፖሊስ አባላት እና የደንብ ልብስ የለበሱ የጥበቃ አባላት ድንጋይ በመወርወር ካስቆሙት በኋላ በዱላ ቀጥቅጠው አቆሰሉት።

በሐምሌ 1935 መጨረሻ ላይ የታይምስ ልዩ ዘጋቢ በይፋ ያልወጣውን ይህን ዜና በማረጋገጥ በሰሜን ምእራብ ኢትዮጵያ /ወልቃይት/ ወይም ዳልኪት (ከጎንደር ሰሜናዊ ክፍሎች አንዱ ነው) በወንዝ ዳርቻ ከትመው ባሉ የጣልያን ወታደሮች ላይ የኢትዮጵያ የጦር አባላት በምሽት ጥቃት ፈጸሙ። ኢትዮጵያውያን የወንዙን አቅጣጫ በመለወጥ ነው በምሽት ያጠቁት። በዚህም አርባ ጣልያናውያንና ሃያ ኢትዮጵያውያን ለሞት ተዳረጉ።

የአውሮፓውያንንና የሌሎችንም ነጮች መብት በተደጋጋሚ በመድፈር ረገድ የኢትዮጵያውያን ብልግና ከመጠን ያለፈ ሆኖ ሳለ ኢትዮጵያውያን "የተጠቃነውና የተደፈርነው እኛ ነን" በማለት ለመጮህ ይሞክራሉ። እስካሁን ለተፈጸሙት ደባዎች ምንም የሚያስተማምን የመፍትሔ ምላሽ አልተገኘም፣ ለወደፊትም ቢሆን ደባው እንደማይፈጸም፣ ጥቃቱም እንደማይቀጥል አንዳች ዋስትና አልተሰጠም።

ጊዜ ባለፈ ቁጥር ኢትዮጵያውያን በተቃራኒው የሚያካሂዱት ድፍረትና ወረራ በመጠንም በአይነትም እየጨመረ የሚሄድ መሆኑ እያጠራጠረም፣

በሥልጣን ላይ ያለው መንግሥት የራሱን ሕዝቦች ለመቆጣጠር ቢፈልግም ምንም ችሎታ የሌለው በመሆኑ ይህ ሁኔታ አይቀጥልም ማለት አይቻልም።

በሚታየው ቸልተኛነት የተነሳ የሰላሙ ዓላማ በክፉ ጎኑ እየተተረጎመ ነው። ጊዜ ባለፈ ቁጥር አደጋውም እየባሰ ይሄድና ኢትዮጵያዊያን ለአውሮፓውያን ያላቸው የጥላቻ መርዝ ወደ አካባቢው አጎራባች ቅኝ አገሮች መሰረጨቱ አይቀሬ ነው።

ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ የኢትዮጵያን ሁኔታ ለመፍታት በኢትዮጵያ ያሉት አውሮፓውያን በመላ ተጨፍጭፈው እስኪያልቁ ድረስ መቆየት አለብን?

፫

# ኢትዮጵያና ሌላው ዓለም፤

ኢትዮጵያውያን በተሻለ መልኩ ለነጮች ዓላማና ምኞት የማይቃወሙና ትእዛዝ ተቀባይ ይሆናሉ የሚል ተሥፋ አለ?

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥትስ እስከዛሬ ድረስ አውሮፓውያንንና ማንኛውንም የአውሮፓውያን የሆነውን ሁሉ ለማንቋሸሽ፣ ለመስደብ፣ በብልግና ለማዋረድና ለጥላቻ ለረጅም ዓመታት ሲያስለጥነው የኖረውን ሕዝብ ወደ መልካምና ጨዋነት መመለስ ይቻለዋል? ከሠለጠኑት አገሮች ሕዝቦች ጋር በእኩልነት ለኖር የሚቻልበት አገርስ መመሥረት ይቻለዋል?

እነዚህ ጥያቄዎች ከመመለሳቸው በፊት ስለኢትዮጵያውያን ተቋም፣ ስለተግባሩ እና ስለ ኢትዮጵያ መንግሥት ችሎታ አንዳንድ መግለጫ መስጠት ያስፈልጋል።

## የኢትዮጵያ መንግሥት መሠረታዊ መመሪያ

ኢቪኒንግ ስታንዳርድ በተባለው ጋዜጣ ላይ (ለንደን የካቲት 1935) ኤቪሊን ዋግህ ባሰፈረው ጽሑፉ ላይ "አውሮፓውያን በምን መብታቸው ነው በኢትዮጵያ የውስጥ ጉዳይ ጣልቃ የሚገቡት?" በማለት ይጠይቅና ራሱ ሲመልስ "የኢትየዮጵያ መንግሥት› በመባል በሚታወቀው በአብዛኛው ግዛት የውጭ ሰዎች የሚባሉትን ጣልያኖች ያህል ኢትዮጵያውያንም የውጭ ሰዎች ናቸው" በማለት ይመልሳል። የንጉሡ መንግሥት በጦር በማስገደድና በጉልበት የተመሠረተ ነው። ንጉሥ ምኒልክ በሕዝቦችና በነገዶች ላይ ግዛቱን ያዋቀረው አንዱ ከሌላው በዘር፣ በሃይማኖት፣ በታሪክም የተለያዩትን በማስገበር ነው። ስለዚህ ኢትዮጵያን ለማስተዳደር ኢትዮጵያውያን ያላቸውን ያህል መብት ጣልያኖችም አላቸው። ኢትዮጵያ በጣልያን መተዳደሯ ከምንም በላይ ጥቅሙ ለኢትዮጵያና ከዚያም አልፎ ለምሥራቅ አፍሪካ ነው…።

ምኒልክ ሁሉንም ሕዝቦች በተከታታይ በመንግሥቱ ውስጥ በማካተት ወደራሱ ሐሳብ የማረካቸውና አንድ ያደረጋቸው ባለው የፖለቲካ ብስለት ነው። በሥልጣኑ መልካምነት፣ በጦርነት ድል አድራጊነቱ፣ "ከሰሎሞን ሲወርድ ሲዋረድ መጣ" በሚባለው ትውልዱ የተረት ተረት ትንግርት ከ1889 ጀምሮ

ኢትዮጵያ በጣልያን ሥር መሆኗን አውልቆ ለመጣል በቃ። ኢትዮጵያ ሙሉ በሙሉ ራሷን በራሷ የምታስተዳድር ሀገር በመሆን መቀጠል የምትችለው ምኒልክ በጠንካራ አመራሩ የመንግሥቱን ቀጣይነት እስካስጠበቀ ድረስ ብቻ ነው።

በ1906 ታላቋን እንግሊዝን፣ ፈረንሳይንና ጣልያንን በወከሉት በግሬይ፣ ካምፓን እና ሳን ጁሊያኖ ለንደን ላይ በተደረሰው ስምምነት መሠረት ውል ተቀባይ አገሮች ነባራዊ ሁኔታው እስከተጠበቀ ድረስ፣ ማለትም ኢትዮጵያ ስርዓቱን የጠበቀች ሀገር እስከሆነች ድረስ እና ከአውሮፓ አገሮች ጋር በወዳጅነት እስከቆመች ውስጣዊና ሌላም ችግር ቢፈጠር ተስማሚዎቹ አገሮች አስፈላጊውን እርምጃ ይወስዳሉ።

ሀገሪቱ በሚከተለው ሁኔታ ተከፋፍላለች :-

እንግሊዝ:- የጣና ሃይቅና የዓባይን መነሻ ጨምሮ የኢትዮጵያን ምእራብ ክፍል፤

ፈረንሳይ:- የፈረንሳይ ቅኝ ከሆነችው ሶማሌ በስተጀርባ ያለውን ሀገር (ማለትም:- በሡልጣኑ የሚገዛውን የአውሳን መሬት እና የሐረርን አውራጃ)፣ የፈረንሳይ እና የኢትዮጵያ የባቡር መስመር እና በሁለቱም አቅጣጫ የባቡሩ ጎማ የሚያልፍባቸውን አገሮች፣

ጣልያን:- በኤርትራ ቅኝ አካባቢ ያሉትን እና የጣልያን ሶማሌን፣ በስተምዕራብ ያለውን ሀገርና አዲስ አበባን የሚያገናኙትን ጠረፎች።[6]

ይህ ሆኖ ሳለ ኢትዮጵያ በተጣደፈ መንገድ ወደ ዓለም ማኅበር መግባቷ የጉዲፈቻ አባት ስለሃብት አወራረስ እንደሚጨነቀው ሁሉ የዓለም ማኅበርም በኢትዮጵያ ጉዳይ በችግር ውስጥ ነው። በውርስ ማስተላለፉ ወቅት የጉዲፈቻው ልጅ ድርሻ ከሌሎች ተወላጅ ልጆች ጋር እንዴት ይሆናል የሚለው የሚያሳስበውን ያህል የአቢሲሲኒያም ጉዳይ አሳሳቢ ሆኗል።

# ኢትዮጵያና የመንግሥታቱ ማኅበር

ኢትዮጵያ ወደ ዓለም ማኅበር አባልነት ስትገባ "ሌላው ቢቀር ከአባል አገሮች የሚጠበቀውን በጣም አነስተኛ የሆነውን መመዘኛ በማሟላት፣ አቅሟ በፈቀደው ሁሉ በግዛቷ ያለውን ሕዝብ ደኅንነት ለማስጠበቅ፣ የሀገሪቱን በጀት ይፋ በማድረግ የዓለም አቀፍ ግዴታዋን በአግባቡ መወጣት እንደምትችል ማረጋገጫ በመስጠትና የወሠኗንም ክልል ወደ ፊት በሚወሰነው መሠረት በመጠበቅ፣ በሀገሪቱ ያለውን የባሪያ ስርዓት ለማስቆም ትችላለች" በሚል አመኔታ ነበር።

አዲስ አበባ የሚገኘው ማዕከላዊ አመራር መደበኛ ተግባሩን በሁሉም የሀገሪቱ ክፍሎች በአግባቡ ማስኬድ አለመቻሉንና የፖሊስ ስርዓቱም መላ

6 በገጽ 6 ላይ ያለውን በካርሎ ሮሲ "storia diplomatic della etiopia" ቱሪን (ሰሜናዊ ምዕራብ ኢጣሊያን ውስጥ የሚገኝ ክፍለ ሀገር) በ1930 የተሠራውን የኢትዮጵያ ካርታ ይመልከቱ።

ቅጡ የጠፋበት መሆኑን በሚከተሉት ገጾች በሚቀርቡት ማስረጃዎች ማረጋገጥ ይቻላል። ኢትዮጵያውያንም ሆኑ የውጭ አገር ዜጎች ለግላዊ ደኅንነታቸውም ሆነ ለሠላማዊ ልማት አንዳችም ዋስትና የላቸውም። የኢትዮጵያ መንግሥት ግዴታውን ለመወጣትና የድንበር ኮሚሽን ለማቋቋም በጣሙን ቸልተኛ ከመሆኑም ባሻገር የተቋቋሙትም በአግባቡ ግዴታቸውን እንዳይወጡ ትልቅ መሰናክል በመሆን ላይ ነው።

በኢትዮጵያ ውስጥ አሁንም የባሪያ ንግድ በሰፊው በመካሄድ ላይ ነው "ባርነት በኢትዮጵያ" በሚለውና በ1934 በታተመው መጽሐፏ እመቤት ሆይ ካተሊን ሲሞን (የእንግሊዝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ባለቤት) በኢትዮጵያ በባርነት ተሸጠው በማገልገል ላይ የሚገኙና ለሽያጭ የተዘጋጁ ሰዎች ቁጥር ከሁለት ሚሊዮን እንደማያንስ ገልጻለች። የባሪያ ሽያጭ ግፍ አሁንም በተረገሙ ኢትዮጵያውያን አዘዋዋሪዎች እንደቀጠለ ነው። እነዚህ ለመከራና ለስቃይ የተዳረጉ ምስኪኖች በሰንሰለት ታስረው ከሀገር ሀገር ለሽያጭ የሚነዱት ከከብቶች ባነሰ ሁኔታ ነው። የባሪያ ንግድ አዘዋዋሪዎች ከንብረታቸው ብዛት የተነሳ እነዚህን ‹ጥቁር የዝሆን ጥርሶች› ጉዘው ሲያደክማቸው ወይም በረሃብ መንቀሳቀስ ሲሳናቸው እስራታቸውን ፈትተው በረሃብ እንዲሞቱ አለያም በአውሬ እንዲበሉ በየመንገዱ ጥለዋቸው ይሄዳሉ። ይህ ትእይንት የኢትዮጵያ መንግሥት "ይህን አስተካክላለሁ፤ ሰብአዊ መብትን አስከብራለሁ" ብሎ ወደ ዓለም መንግሥታት ማኅበር ከገባ በኋላም እየታየ ያለ እውነታ ነው።

ይህን መሳዩ አረመኔያዊ ተግባር ራሳቸውንና ሕዝብን አክብረው ከሚያስተዳድሩ አባል አገሮች እምነት ውጪ ነው። በኢትዮጵያ የሚኖሩ ነጮች ይህን ግፍ ሳይወዱ እየተመለከቱ እንዲኖሩ ተገድደዋል፤ የእነሱ ኑሮም ከባርነት ያልተሻለ ነው። ከጎረቤታቸው እየተሰረቁ ወደ አረብ አገሮች የሚሸጡ ሕጻናት በኢትዮጵያውያን የባሪያ ነጋዴዎች የሚደርስባቸውን ግፍና መከራ ማየቱ የሚዘገንን ነው። ይህ ሁሉ ድርጊት የሚፈጸመው የዓለም መንግሥታት ማኅበር አባል በሆነችውና "ኢትዮጵያ" በምትባለው የመከራና የረሃብ ሀገር ነው።

ትልቁ ጥፋት ደግሞ ጉዳዩን ለማጣራት ተብሎ የምስጢር የኮሚሽን አባላትን በ"እንግሊዝ ባርነትን ለመዋጋት ማኅበር" ወደ ኢትዮጵያ መላካቸው ነው። የኮሚሽኑ አባላት አንዳችም የሀገሪቱን ቋንቋ መናገርና መስማት ሳይችሉ ነው ለዚህ ተግባር የተላኩት። የዚህን ተግባር ሪፖርትም ለዓለም ማኅበር አስገብተዋል። ሎርድ ኤን በክስተን ከዘመዱ ካውንት ኤ ቢና ከደችላንዱ ጀ ኤን ጋር በአዲስ አበባ አካባቢ ሲዘዋወሩ ነበር። በየደረሱበት ሁሉ ያዩትን ሰው "ይኸ ባሪያ ነው" በማለት በእጃቸው እያመላከቱ ሲጠይቁ ነበር፤ ግን አንዳችም የአገሪቱን ቋንቋ አይችሉም። በዚህም ራሳቸውን መሳለቂያ አድርገው ቆዩ። በኢትዮጵያ ቆይታ ያደረገ አለያም ወደ ደቡብ የተጓዘ ማንም ግለሰብ ከቡርነታቸው ካወቁት በላይ በኢትዮጵያ ስላለው የባሪያ ንግድ ስርዓት ሊረዳና ሊያስረዳ ይችላል።

በምሥራቅ አፍሪካ ሰላማዊ ሰዎች ሰላማቸውን እንዲያጡ በሚደረግበትና አረመኔዎች ማንንም እንደከብት በሚነዱበት ስርዓት አድነውም ሆነ በአጋጣሚ በእጃቸው የገባውን ፍጡር ሁሉ ለሰለባ በሚዳርጉበት ሁኔታ ጨርሶ ሰላም ሊገኝ አይችልም። ይህንን ድርጊት ለማስቆም በሚገባ የሠለጠኑና ስርዓት የተማሩ፣ በአውሮፓ ደረጃ የተሟላ ትጥቅና ስንቅ ያላቸው የጦር አባላት መሠማራት አለባቸው። ይህን አይነት ተግባር ለሚፈጽሙ አገሮች የመንግሥታቱ ማኅበር ቦታ ሊቸራቸው አይገባም። በመጠጥ መቸርቸሪያ ቦታዎች የቀይ መስቀልን አርማ አላግባብ በመስቀል የሚነግዱ አባል አገሮችን ሕጉ አንድ ሊላቸው ተገቢ ነው። ይህ ድርጊት በኢትዮጵያ "ጠጅ ቤቶች" የሚታይ እውነታ ነው።

## ኢትዮጵያና የውጭ ኃይሎች

ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ኢትዮጵያ ወደ ዓለም ማኅበር እንድትገባ ድጋፋቸውን በቸሩት አገሮች ላይ የጥላቻ ቅስቀሳ እየነዛች መሆኗ ቀደም ብሎ ተወስቷል። እስካሁን ድረስ ኢትዮጵያውያን ካላቸው መመሪያ በተቃራኒው በፍላጎታቸው መሠረት ለውጭ ሰዎች መሬት በኮንትራት ለመስጠት ፈቃደኛ አይደሉም። በወሠን አካባቢ በኢትዮጵያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትርና በጃፓን መንግሥት መካከል በምስጢር በተደረሰ ስምምነት መሠረት ኢትዮጵያ ለጃፓን ቅኝ ገዢ አራሾች 41/2 ሚሊዮን ኤከር (የአንዱ ኤከር ስፋቱ 4000 ሜትር) አዘጋጅታለች። በዚህ ቦታ ላይ የጃፓን ገበሬዎች ጥጥ እና እንደ አሜሪካን ዘገባ[7] አደንዛዥ እጽ (ኦፒዩም) እንዲያመርቱ ተፈቅዶላቸዋል።

የነዚህ የሁለቱ አገሮች መፈቃቀድና መቀራረብ ለአውሮፓውያን ኃይል በእጅጉ አሳፋሪ ነው። በሁለተኛ ደረጃ ደግሞ የዓለም ማኅበሩ አባል የሆነች ሀገርና የማኅበሩም ሕገ ደንብ የኦፒዩምን ምርት አጥብቆ የሚዋጋ በመሆኑ ድርጊቱ ሊፈቀድ አይገባም ነበር።

በአውሮፓውያን ኃያላን መንግሥታት ላይ ኢትዮጵያ የምታካሂደው ጎጂና ሕገወጥ ድርጊት እየጨመረ በመሆኑ ወደ ሌላ አቅጣጫም ሊሄድ እንደሚችል ግንዛቤ ሊደረግበት ይገባል። አሁንማ ጃፓኖች በኢትዮጵያ የቀረጥና የፖስታ አገልግሎት መሥሪያ ቤት፤ በሌሎችም የቅርንጫፍ ቢሮዎች ሥራ እየተሰጣቸው ነው። አንድ የጃፓን የመሐንዲሶች ኮሚሽን የአውሮፕላን ማረፊያ ጣቢያ እንዲያዘጋጅ ኃላፊነት ተሰጥቶታል። መጠነ ሰፊ የጦር መሣሪያም ከጃፓን ለመግዛት ድርድር በመካሄድ ላይ ነው።

የአውሮፓ ኃይላትም ጃፓን ወደ ሁሉም የኢትዮጵያ ግዛቶች የምታስገባውን ምርት በመታገስ፤ የአሜሪካንንና የአውሮፓን ንግድ እየተጫነው እንደሆነ ማስጠንቀቂያ ሰጥተዋል። ይህን ሁኔታ ለመዋጋት አስፈላጊው እቅድ ሊነደፍና ሊተገበር እንደሚገባ፣ ኢትዮጵያ ነጮችን ከግዛቷ ጠራርጋ ለማስወገድ ያላትን ዓላማ ማክሸፍ ተገቢ እንደሆነ ጠቁመዋል። ይህ ሁሉ ቢደረግም የኢትዮጵያ መንግሥት የሚመለከታቸውን የአውሮፓ የዲፕሎማቲክ ማኅበረሰብ አባላት

7 "ኮሎምቢያ" ዊኖና-ሚሊዋኬ-ቅዱስ ሉዊስ ቁጥር 52 (ሕዳር 1935)።

ሳያማክር 20 ገጽ ያለው አዲስ የታክስ ታሪፍ ሲያወጣ ታሪፉ ከጃፓን በሚመጡ ምርቶች ላይ ከፍተኛ ቅናሽ እንደሚደረግ ይደነግጋል።

በኢትዮጵያና በጃፓን መኻል የኢኮኖሚ መግባባት ተመስርቶ፣ በሁለቱ አገሮች ሕዝቦች መኻል ጋብቻ ለመፈጸም እቅድ ወጥቶ፣ 2000 የሚሆኑ ጃፓናውያን አምራቾች ከኢትዮጵያውያን ሴቶች ጋር ጋብቻ ሊመሠርቱ ነው። የዚህ ፖሊሲ መታወጅ ለአመራር የሚበቁ ጥቂሮችን ለመፍጠር የሚያስችል በነጮች ላይ የታሰበ ሤራ ሲሆን፣ ተግባራዊነቱም በጃፓኑ ልዑል ኩራዶ ልጅና በኢትዮጵያዊው ልዑል አየለ ልጅ መኻል በሚፈጸም ጋብቻ ሊበሠር ታቅዷል። ሆኖም በመጨረሻው ሰዓት ጣልያን ይህ ስምምነት እንዳይፈጸም ማድረግ መቻሏ ይነገራል።

የግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ መንግሥት የማይተኩትን የአውሮፓ አማካሪ ባለአደራዎችን በማባረር በቦታቸው ጃፓናውያንን እየተካ ነው። ጃፓናውያን በሀገራቸው ካለው የኑሮ ዝቅተኛነት የተነሳ ርካሽ ዋጋ ከማስከፈላቸው በተጨማሪ በኢትዮጵያውያን የበለጠ አመኔታ ስለሚሰጣቸው በጋራ ጠላቶቻቸው /የነጭ ዘር/ ላይ አብረው መቆማቸውም የመወዳጀታቸው አንድ ምክንያት ነው።

በኢትዮጵያ ሲቪል አገልግሎት ውስጥ አማካሪዎችንና ባለሙያዎችን የመመደቡ ጉዳይ እስካሁን ድረስ በአውሮፓውያንና በአሜሪካውያን ብቻ ተይዞ ነበር። አሁን ግን ይህ ሁሉ አደጋ ላይ እየወደቀ ነው። የኢትዮጵያ መንግሥት የተመዳቢዎቹን ቁጥር ሆን ብሎ ከሦስቱ ኃያላን መንግሥታት፣ ማለትም አጎራባች የቅኝ ግዛት ድንበር ካላቸው እንግሊዝ፣ ፈረንሳይና ጣልያን በጣም በመቀነስ ከአውሮፓ አገሮች ጋር ፍላጎቱን አዳብሯል።

ወታደራዊ ተቋማትን የማደራጀቱና የማሠልጠኑ ተግባር በመጀመሪያ ለስዊዘርላንዶች፣ ቀጥሎ ለቤልጅጎች፣ በመጨረሻም ለስዊዲኖች[8] ተሰጠ። ቤልጂጎች ለፖሊስ ኃይሉ ክፍልም ፍላጎት አድሮባቸዋል።

የስዊድን ወታደራዊ ተልእኮ (ሚሲዮን) በኢትዮጵያ የመመደቡ ስምምነት ሰበቡ በንጉሡና በስዊዲን ቆንሲል ዶ/ር ካርል ሐነር መኻል ያለው ወዳጅነት ነው። ቆንስሉ በ1933 ስዊድን ነበርና የስልጠናውና ብዙ የተወራለት የስዊድኑ አልጋ ወራሽ ጉብኝት ጉዳይ በጄኔራል ቨርጂን እንዲመራ ተደረገ። የስዊድኑ አልጋ ወራሽ ጉብኝትም ኢትዮጵያውያን የነበረባቸውን ቅሬታ ሁሉ ለማስማት ምቹ ሁኔታ ከመፍጠሩም በላይ ሕብረተሰቡን በቀላሉ ለማግባባት ተጠቀሙበት። በመጨረሻ ትኩረት ሊሰጠው የሚገባው ጉዳይ ከተለያዩ የውጭ ተወካዮችና ከኢትዮጵያውያን ጋር የሚፈጠር ወዳጅነት ሁሉ ከሌሎች ቦታዎች የበለጠ ወሳኝነት ሊኖረው የሚችለው ቦታ አዲስ አበባ መሆኑ ነው።

በአጠቃላይ "በውጭ ኃይላት ጥበቃ እናገኛለን" በማለት የተማመኑት ናቸው ይህን ሁሉ መከራ መቻል ያለባቸውና በኢትዮጵያውያን በሚሰነዘርባቸው ጥቃት በሚያሳዝን ሁኔታ ተጎጂ የሚሆኑት። መልካሙ ግንኙነት በነጮች ላይ

8 የኢትዮጵያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ቢሮ አማካሪ የነበረው ዶ/ር ኮሎሙዲን በ1933 ዓ.ም. ሲሞት በቦታው አሜሪካዊው ፕሮፌሰር ኤርነስት ዎርከ ተተከቶ በመንግሥታቱ ማኅበር ኢትዮጵያን ወክሎ ሠርቷ።

ለሚፈጸመው ደባ ማካካሻ ሆኖ ከኢትዮጵያውያን ጋር የሚደረገው ሙግት ድጋፍ አያገኝም። በየኢምባሲው ቢሮዎች፣ ሁለገብ ሠራተኞች የሆኑና ዘራቸው የሚያጠራጥር ሰዎች ለዘመናት ቋሚ ንብረት በመሆን፣ በኢምባሲያቸውና በኢትዮጵያውያን መንግሥት መኻል በማስተርጎም ተግባር ይኖራሉ። እነዚህ ሰዎች ባላቸው አገራዊ ጉዳይ ቋንቋውን በማወቃቸው፣ በሚሰየመው የጋራ ችሎትም ቆንስላዎችን ወክለው ይቀመጣሉ። ስለዚህም አንድ ነጭ በሀገሬው ሰው በምቀኝነትና በማጭበርበር ስሜት ክስ ቢመሠረትበት ጉዳዩ በኢትዮጵያዊ የመኻል ዳኝነትና በኤስያዊ ገምጋሚነት ነው የሚታይለት።

በኢትዮጵያ የሚኖሩ አውሮፓውያን ሁሉ ተገቢ አስተዳደር እንዲያገኙና ሕግን ለማስተካከል እንዲቻል ኢትዮጵያ በእንግሊዝ ሞግዚትነት ልትተዳደር ይገባል።

የዲፕሎማቲክ አባላት በኢትዮጵያ ጉዳይ ላይ ሁሌም የተቃውሞ ስሜት አያሳዩም። የአውሮፓውያንን ኅብረት ያጣው ኃይላቸው የበረታ ውጤት ሊያስገኝ አልቻለም፤ ስለዚህ ነገሩ ሁሉ የዲፕሎማቲክ ጓዶች የፖለቲካ ጽድቅ “Laisser Faire, Lassier passer” ሆኗል።

በአዲስ አበባ ያሉት ሌጋሲዮኖች ያለፉትን ዓመታት የቸልታ ኃጢያት ፍሬያቸውን እያመረቱ ነው። ሊከሰት በሚችለው የኢትዮጵያውያንና የአውሮፓውያን ግጭትም የውጭ ቆንስላዎች ሁኔታ አጠራጣሪ ነው። የእንግሊዝ ሌጋሲዮንን ደኅንነት ለማጠናከር 150 የሕንድ ወታደሮች ወደ አገር ውስጥ እንዲገቡ የኢትዮጵያ መንግሥት ፈቃድ ተጠይቆ ነበር። ሌሎች ተመሳሳይ ጥያቄዎች መልስ ቢያጡም ለእንግሊዝ ግን የውለታ ምላሽ በሚመስል መልኩ ተፈቀደ። በሌላ በኩልም ጥበቃን በተመለከተ መንግሥት ኃላፊነት እንደሌለበትና የግቢ ጥበቃም በየግል የሚከናወን መሆኑን አስታወቀ።

# የንጉሠ ነገሥቱ የሰለሞን ስርወ መንግሥት እና መሠረታዊ ሕጋዊነት

በውጭ መንግሥታት የተከበረውና አሁን የተገባው ውል ጣልቃ የመግባትን መብት የሚፈቅድ ቢሆንም የአውሮፓ መንግሥታት ተወካዮች ስምምነት በማጣታቸው የተነሳ ያለምንም ተቃውሞ የኃይለ ሥላሴን ወደ ሥልጣን መውጣት ተቀበሉ። የምኒልክ ወራሽ በሆነችው በንግሥት ዘውዲቱ የግዛት ዘመን በልዑል ራስ ተፈሪ መኮንን ድጋፍ ከዙፋን የወረደው ትክክለኛው ወራሴ መንግሥት ልጅ ኢያሱ በተንኮልና በሴራ መብቱን ተገፍፎ እስካሁን ድረስ ለዓመታት በእስር ላይ ነው።

የወሎ ኦሮሞ ተወላጅ የሆኑትና ትውልዳቸውን ከምሥራቅ አረቢያው የሙስካት ኢማም የሚያጣቅሱት (በኋላ ከእስልምና ወደ ኦርቶዶክስ እምነት የተገለበጡት) የንጉሥ ሚካኤል ልጅ ኢያሱ በሰኔ 1908 ባለሙሉ ሥልጣን

በተቀመጠው ገዢ በራስ ደሥታ ዳምጠው እንዲተዳደር ሆኗል። በሌላም በኩል ንጉሡ የጎጃሙን ራስ ኃይሉን ከዙፋኑ በማውረድ እስር ቤት ዶሎታል።

ትኩረት ሊደረግበት የሚገባው ዕውነታ ያሁኑ ገዢ ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ላለፉት ሃያ ዓመታት ሕጋዊውን ዘውድ ጫኝ ልጅ ኢያሱን[10] ከሥልጣን ሲያባርር፣ በዘር የተላለፈለትን የጎጃሙን ራስ ኃይሉን ለሞት ሲዳርገው፣ ሌላም ብዙ ተመሳሳይ ድርጊት ሲፈጽም የኢትዮጵያ ባለሥልጣናት “የሀገሪቱን አንድነት ለመጠበቅ” በማለት መተባበራቸው ንጉሡ የአገሪቱን ሀብት ለግሉ እንዲያግበሰብስ ዕድል ሰጥቶታል።

በማንኛውም መንገድ ማንም ከኢትዮጵያ ሁኔታ ጋር የሚተዋወቅ ሰው ሊክደው የማይችለው፣ የንጉሥ ኃይለ ሥላሴ የበላይ ገዢነት ሕጋዊነት የሌለው በዘር ሕግም ተቀባይነት የማያገኝ አለያም የሕዝብን ልብ ያሸነፈ አለመሆኑን ነው።

## የአንድነቱ ችግርና ውስጣዊ አስተዳደር

የአዲስ አበባ ገዢዎች “የኔ ነው” በሚሉት ግዛት 12 ሚሊዮን ነዋሪዎች ሲኖሩት፣ 40 በመቶው ክርስቲያን ሲሆኑ፣ 40 በመቶው የእስልምና ተከታዮች፣ 15 በመቶው ደግሞ አረመኔዎች ናቸው። ቀሪው ይሁዳውያን፣ የሮማ ካቶሊኮች እና የፕሮቴስታንት እምነት ተከታዮች ናቸው።

ከዘር አንጻር የአማራው ገዢ መደብ (የመካከለኛውን የሀገሪቱን ክፍል የሚይዘው)፣ ኦሮሞዎች፣ ጎጃሚዎች፣ እና የትግሬ ነገዶችን ያካትታል። አፋሮች እና ሶማሌዎች በምሥራቃዊው ክፍል ይኖራሉ። በተለይ በምዕራቡ ክፍል ብዙ ዘር ያላቸው ሕዝቦች ይገኛሉ።

የእያንዳንዱ አካባቢ ሕዝብ አንድ የሚሆነው በአብዛኛው በሚናገረው ቋንቋ መሠረት ሕብረት በመፍጠር ነው። እነዚህ አካላት የሚተዳደሩት በዘር በሚተላለፉ ሹሞች ሲሆን፣ እነሱም የኢትዮጵያ ፌዴራላዊ መንግሥት መሠረቶች ናቸው። የክርስቲያኑ አካባቢ ሹሞች (ለምሳሌ የአክሱም እና ጎንደር) እንዲሁም አረመኔያዎቹ ከፋዎች ይታወቁ የነበሩትና አሁንም የሚታወቁት “ንጉሥ” ወይም “ራስ፣ ልዑል” የሚል ማዕርግ በአላቸው ሹሞች ነው። የመሐመዳውያን ልዑላን ደግሞ (ለምሳሌ ሐረር፣ ጂማ፣ አዋሳ፣ ቤንሻንጉል...) “ሱልጣኖች” ይባላሉ። ቀሪዎቹ በንጉሡ መልካም ፈቃድና ሹመት “ደጃዝማች” ተብለው ይገዛሉ።

10 በኢትዮጵያ ፖለቲካዊ ምሥጢር ላይ በቂ እውቀት ያለው ሄንሪ ደ ማንፍሬዲ የተባለ ጸሐፊ “ጋራ ሙለታ አሉ” የተባሉት ልጅ ኢያሱ በጥንቃቄ በተዘጋጀ አደንዛዥ ዕፅና መረዥ ቅጠላ ቅጠል በ1934 ለሞት እንደተዳረጉ ጽፏል። ይሁንና በቅርቡ እንደሚናፈሰው አሉባልታ የሀገሪቱ እስረኛ የሆኑት ኢያሱ ምሥጢራዊ በሆነ መንገድ ከጥቂት ወራት በፊት ከአዲስ አበባ በስተምዕራብ 35 ማይልስ ርቀ ወደሚገኘው አዲስ ዓለም መወሰዳቸው ይደመጣል።

የያንዳንዱ ክልል ውስጣዊ አስተዳደር አንዱ ከሌላው የሚለይ ሲሆን ከሞላ ጎደል በፊውዳሉ ሥርዓት ላይ የተመሠረተ ነው። ሹሞቹ ወታደራዊ ገዢዎችም ናቸው። የሲቪሉን አስተዳደርም ለጓደኞቻቸው፣ ለወዳጆቻቸው፣ ለዘመዶቻቸውና የኢትዮጵያውያን ባላባቶችን ፈቃድ ለሚጠብቁትና ለሚያስጠብቁት አገልጋዮቻቸው ያድላሉ። የኋላ ኋላ ማዕከላዊ መንግሥት በየቦታው በማቆጥቆጥ ላይ ያለውን ሌብነትና ሕገ ወጥነት ለመቆጣጠር ቢያንስ በመኻል የሀገሪቱ ክፍሎች ፖሊስ ጣቢያዎችን በማቋቋም ላይ ነው።

በሁሉም የሕዝቡ የኑሮ አቅጣጫ ላይ አስተዳደሩን ከመኻል ወደ ዳር የማሰራጨቱ ሂደት አንድ አይነት ይዘት እንዲኖረው ጠንካራ ፍላጎት እየታየ ነው። ሆኖም ሥርዓትን ማስተካከል፣ የደኅንነት ዋስትና መስጠት፣ አዲስ አበባ ሆኖ ፍትሕንና ደንብን በሀገሪቱ አጠቃላይ ሥፍራዎች ማስፈን አይቻልም።

ማዕከላዊው መንግሥት በመኻል የሀገሪቱ ክፍሎች የመቆጣጠር ኃይልም ሆነ ሥልጣን የለውም። ለምሳሌ አንድ የውጭ ተወላጅ ወደ መኻል ሀገር ጉዞ ከመጀመሩ አስቀድሞ ልክ ከሀገር ውጪ እንደሚጓዝ አይነት፣ አዲስ አበባ ከሚገኘው የውጭ ጉዳይ መሥሪያ ቤት የንጉሠ ነገሥቱ ማሕተም ያረፈበትን ልዩ ፓስፖርት ማውጣት ይጠበቅበታል። ይህ የሚያረጋግጠው የአዲስ አበባው መንግሥት ራቅ ባሉት የሀገሪቱ ቦታዎች ላይ ኃይል እንደሌለው፣ ይልቁንም በየአካባቢው ባለሥልጣናት ላይ ጥገኛ መሆኑንና የውጪውን ተጓዥ ለአካባቢው ሹማምንት አደራ መስጡትን ነው።

በኢትዮጵያ ያለ እያንዳንዱ ነጭ ይኸ ፓስፖርት ዋጋ ቢስ መሆኑን ያውቃል። ከዋና ከተማው በ10 ማይልና በባቡር መስመሮቹ አቅጣጫ የሚገኙ የአካባቢው ባለሥልጣናት ማሕተሙን ባዩ ጊዜ አክብሮት መሰል ሠላምታ ያሳያሉ። ወዲያው ግን የንጉሠ ነገሥቱን ማሕተም ማሳየት የሚያስገኘው ጥቅም ሳቅ፤ አለያም “ኃይለ ሥላሴ? አናውቀውም! መልካም ፈቃድህ ሆኖ በማን ባላባትነት ስር እንደሆንህ ብትነግረኝ” የሚል ፌዝ ብቻ ነው።[11]

በፍርድ ቤቶች አካባቢም ተመሳሳይ ሁኔታ ነው የሚያጋጥመው። ለምሳሌ በሰላሌው ችሎት ተቀባይነት ያለው ብቸኛ የመሐላ ቃል የአካባቢውን ባለሥልጣን ራስ ካሣን በማንሳት “በካሣ ሞት” ማለት እንጂ የንጉሠ ነገሥቱ ስም ጨርሶ አይነሳም። በአጋጣሚ “በኃይለ ሥላሴ ሞት” ቢባል ችሎቱ በጠቅላላው ሳቅ በሳቅ ይሆናል።

የንጉሡ ሥልጣን ብዙ ጊዜ የሚከበረው ጥብቅ በሆነ እርምጃ ብቻ ነው። በሚያማምሩ ቃላት በተከሸኑ አገላለጾች “የኢትዮጵያ ሕዝቦች ከውጭ የሚሰነዘርን ጦርነት ለመመከት፣ አለያም ሀገርን በሚመለከት ጉዳይ ላይ እንደ አንድ ሰው ናቸው” በማለት የሚገለጸው ሕዝቡ የማያምንበት አባባል ነው። ሕብረት የሌላቸው መሆኑን ማረጋገጫው በሰኔ 1935 መጀመሪያ ላይ የንጉሠ ነገሥቱ ባቡር በኢትዮጵያ ግዛት መኻል ሲያልፍ ከፍተኛ ቁጥር ያለው የአፍደም አካባቢ ነዋሪ በባቡሩ ላይ ያደረሰበት ጥቃት ነው።

11 ካውንት ሉዊ ሃይን “ከአዲስ አበባ የተደረገ የአራት ቀን ጉዞ” በሚለው መጣጥፉ “በኢትዮጵያ ድቅድቅ ጫካ ውስጥ ሰዎችና እንስሳት” (1934፡52)

እንደ እውነቱ ከሆነ "የተባበረ ኢትዮጵያዊ" የሚባል ነገር የለም። ይልቅስ 20 በመቶ የሚሆነው አናሳ የአማራ ሕዝብ በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ የሚኖሩትን ሕዝቦች በራሱ ወጥመድ ውስጥ በማጥመድ፣ ጉልበቱ እስከፈቀደለትና ማግባቢያው እስከረዳው ድረስ በባርነት ማነቆ ወጥሮ መግዛቱ ነው። በኢትዮጵያ ያሉት ክርስቲያን ያልሆኑ ሰዎች ከአማራ ጭቆና ለመላቀቅ ካላቸው ፍላጎትና ምኞት የበለጠ ምንም ነገር የላቸውም። በነጻነት ድምጽ የመስጠት መብት ቢሰጣቸው አሁን ካሉበት የከፋ የጭቆና ኑሮና ዓለም ካወገዘው የባርነት አገዛዝ ወጥተው በአውሮፓውያን ሞግዚትነት መተዳደርን ይመርጣሉ።

በ1930 በኦሮሞዎች፣ በ1932 በጎጃሞች የተካሄደው የመብት ጥያቄ አመጽና ሕጋዊ ንግሥናውን የተነጠቀውን ልጅ ኢያሱን ከሰላሌ/ፍቼ ለማስመለጥ የተካሄዱት ቁጥራቸው የበዛ ሁከቶች የኢትዮጵያ ግዛት ስለሚባለው ሀገርና የይስሙላ አንድነት ያስረዳሉ። ሀገሪቱ በመገጣጠሚያዋ ላይ ሁሉ መለያየት እያጋጠማት ነው፤ እስካሁንም በአንድነት ልትቆይ የቻለችው በማይረባና ዘላቂነት በማይኖረው የጦር፣ የስለላ ተቋምና የፖሊስ ኃይል ነው።

ከሕጋዊው የዘውድ ወራሽ ከልጅ ኢያሱ ጋር ታማኝነታቸውን በመሐላ ያረጋገጡት ሹማምንት ከንጉሡ ጋር ለእስር ከመዳረጋቸውም በላይ በጦር ወንጀለኛነት ተፈርጀው ለፍትሕ አልባ ሞት ተዳርገዋል።

ይህን ተግባር የፈጸሙ ሰዎች በየወሰኑ ላይ የሚያካሂዱትን ጥቃት እና የውጭ ዜጎችን የመግደልና የማንገላታት ሁኔታ "መቆጣጠር ይችላሉ" ማለት አይቻልም። ከ1933 እስከ 1935 የነበሩት ወቅቶች የዚህ ድርጊት ማስረጃዎች ናቸው።

ስለዚህም የኢትዮጵያ መንግሥት አስፈላጊ የሆነው የሉዓላዊ መንግሥትነት መሠረት ማለትም በውስጥ የአስተዳደር ችግር የወሳኝነት ኃይልና ሥልጣን የለውም።

## ጥምር "ልዩ ፍርድ ቤት"፣ የቆንስላ ሥልጣንና የቆንስላ ልዩ ፍርድ ቤት

በኢትዮጵያ ያለው ፍትሕ የማግኘት ሂደትና አስተዳደር ይቺን ሀገር ማንኛውንም መብት በእኩልነት ከማግኘት ለማገድ የሚያስችል በቂ ማስረጃ ነው። ተወላጅ የሆኑት ዳኞች የሚያስተላልፉት የተዛባ ፍትሕ፣ የሚያደርሱት ፍትሕ አልባ በደልና አድልዎ፣ ግድየለሽነት፣ ሙስና፣ በብዛት የሚታየው አለመተማመን፣ ወዘተ በየወቅቱ እየተባባሰ ነው።

በ1908 በጸደቀው የክሎበውስኪ ስምምነት፤ ለቆንስላ ልዩ ፍርድ ቤት፣ የመኖሪያ ፈቃድ ላላቸው አባላት፣ በቅድሚያ ለፈረንሳውያን፣ ከዚያም ለተመረጡ አገሮች ዜጎች እና ከኢትዮጵያ ጋር የዲፕሎማቲክ ግንኙነት ላላቸው አገሮች በሕጉ ላይ በጽሑፍ በሰፈረው መሠረት ባለሥልጣናቱን ወደ አውሮፓ ደረጃ ለማቀራረብ፣ ለማስተማርና ለማሠልጠን ሥልጣን ተሰጥቶ ነበር።

በቻይናና በኢራቅ ከተወገዘና ከታገደ በኋላ የቆንስላ ልዩ ፍርድ ቤት ያለው በንጉሡ ሀገር ብቻ ነው። በአንቀጽ 7 ላይ በሰፈረው ስምምነት መሠረት የእጅ መስጠት ግዴታ እንደሚያስረዳው፤ ማንኛውም የወንጀልም ሆነ የፍትሐ ብሔር ጉዳይ የሲቪልና የዲፕሎማቲክ ግንኙነት ያላቸውን አገሮች ሰዎች የሚመለከት እስከሆነ ድረስ ተጠያቂዎቹ ወይም ከሳሾች የውጭ አገር ሰዎች ከሆኑ የቆንስላው ተወካዮች በሚገኙበት ችሎት ይካሄዳል።ጉዳዩ የውጭ ዜጎችንና የንጉሡን ዜጎች የሚያሟግት ሆኖ ሲገኝም "ልዩ ፍርድ ቤት" ተሠይሞ በንጉሡና በውጭ ዜጋው ቆንስላ ወይም ውክልና ባለው በምክትሉ ስምምነት መሠረት ፕሬዝዳንቱ ይሾማል።

የኢትዮጵያ ፖሊስ ወንጀል ሲሠራና ደንብ ሲጥስ ያገኘውን የውጭ ዜጋ የማገት መብት ሲኖረው ጉዳዩንም ለታጋቹ ዜጋ ቆንስላ የማሳወቅ ግዴታ አለበት።

ስለ ልዩው ፍርድ ቤቱና በችሎቱ አካሄድ ላይ ስለሚኖረው ሥነ ሥርዓት አንድ ስምምነት ላይ ለመድረስ ለዓመታት ጥረት ተደረጎ ነበር፤ ነገር ግን የኢትዮጵያ መንግሥት እነዚህ ልዩ ፍርድ ቤቶች በአግባቡ ሥራቸውን እንዲያከናውኑ አይፈልግም። የኢትዮጵያ መንግሥት ይህን አይነቱን አካሄድ እንዲተው በመቃወም የውጭ ሌጋሲዮኖች ወኪሎቻቸውን ለመላክ ፈቃደኛ ባለመሆናቸው ፍርድ ቤቶቹ እንዲዘጉ ሆኗል።

ቁጥር ስፍር የሌላቸው በዓላትና የማያልቀው የቀጠሮ ብዛት፤ ኢትዮጵያውያንን በጥፋታቸው መጠን እንዳይቀጡ ይከላከልላቸዋል። በሀገሬው ሰዎች የሚቀርበው ረጂሙና ውስብስቡ ክርክር በአማርኛ ቋንቋ እና በሌሎችም የተለያዩ የሀገሪቱ ቋንቋዎች በአግባቡ ስለማይተረጎም ተአማኒነቱ በእጅጉ አጠራጣሪ ነው። በነጮች የተጠሩት ምስክሮች በተለያየ ሰበብ እንዳይቀርቡ ለማድረግ "መኖርያ አድራሻ ሊኖር ይገባል" የሚል ምክንያት ይደረደራል።በአዲስ አበባ ካሉት መንገዶች በጣም ጥቂቶቹ ናቸው ለአድራሻ ማስመዝገቢያ ብቁ የሆነ ስም ያላቸው፤ ቤቶቹም ቁጥር የላቸውም። ነዋሪዎች ሁሉም ማለት በሚያስችል መልኩ መሐይሞች ናቸው። በአንጻሩ እያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ የየአንዳንዱን የውጭ ዜጋ መኖሪያውን በሚገባ ስለሚያውቀው ለማግኘት ችግር የለውም።

የተለያዩ የጎሳ አባላት በነጮች ላይ በሚሰጡት ምስክርነት በአብዛኛው በነጮቹ በኩል ተቀባይነት የለውም። ቃለ መሐላቸውን የሚፈጽሙትም መጽሐፍ ቅዱስ ወይም ቁርዓን ጨብጠው ነው። የሚመጡት ከወህኒ ቤት በመሆኑና ምስክርነታቸውም ከተፈረደባቸው ቅጣት ቅናሽ ለማግኘት በሚገባላቸው ቃል ስለሆነ፤ የቆንሲሎቹ ጠበቆች በመስቀልኛ ጥያቄ ወጥረው በመያዝ ተቀባይነት ያሳጧቸዋል።

የችሎቶቹ ሂደቶች ምንግዜም ለሕዝብ ክፍት አይደሉም። ችሎቱን የሚያስተናግዱት ፖሊሶች ለእያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ ባለሥልጣን በሩን ከፍተው፤ እጅ ነስተውና ተሽቆጥቁጠው ሲያስተናግዱ፤ የችሎቱን ሂደት

ለመከታታል የሚመጡትን ነጮችና አጋሮቻቸውን ግን አያስገቧቸውም፤ ይህም መንግሥታዊ መመሪያ ያለበት ይመስላል።

በሌላ ጎኑም የነጮችና የሀገሬው ተወላጆች በችሎት ፊት ያላቸው መስተንግዶ እኩል ያለመሆኑ ይፋ እየሆነ ነው። ለምሳሌ የሀገሬው ከበርቴዎች አሽከሮች አለያም አንጋቾች ጌቶቻቸውን ወደችሎት አጅበው እንዲገቡ ሲያስፈልግም በችሎት እንዲወከሏቸው ሲፈቀድላቸው፤ ለውጭ ዜጎች፣ ወዳጆቻቸውና የሕግ አማካሪዎቻቸው ግን ይህ እድል አይሰጣቸውም። እኔና የቀድሞው የሁንጋሪያው የፓርላማ አባል ኤፍ ኤ በ1933 ነሐሴ 17 በምክር ቤቱ ፕሬዚዳንት በቢትወደድ ወልደጻድቅ ጉዳይ ተከስሰን የተሚገትነውም በዚህ ሁኔታ ነበር።

አውሮፓውያን ያላቸው የአማርኛ ችሎታና የሕጉን ትርጉም ለማግኘት ያለው ችግር ነጮችን ለተዛባ ፍርድ ይዳርጋቸዋል። የችግሩ ውስብስብነት ለቁጥር የሚያዳግት ነው፤ ለምሳሌ "ተመጣጣኝ" የሚለው ቃል ለችሎቱ የመጠራጠር እድል ይሰጠውና ባሕልና በኢትዮጵያ ሕግ መሠረት ለኢትዮጵያዊው ከሳሽ እንዲፈረድለት ይረዳዋል።

በመጨረሻም ግልጽ የሆኑ የክስ ጭብጦች በኢትዮጵያውያን ባለሥልጣኖች ተቃውሞ ይደረግባቸዋል። አውሮፓዊው ምንም ያህል እውነት ቢኖረው ኢትዮጵያዊው ባለሥልጣን "እቃወማለሁ" የማለት መብት አለው። ተከሳሹ ከሚመለከተው የሚኒስቴር መሥሪያ ቤት ጋር መግባባት ከሌለው በስተቀር ሕጉ በአግባቡ "ተተርጉሞ ሚዛናዊ ውሳኔ አገኛለሁ" የሚለውን ተሥፋውን ቢረሳው ይሻለዋል። በኢትዮጵያውያን በተደጋጋሚ የሚነገሩት "እሺ፣ ነገ" የሚሉት ቃላት ጉዳዮችን ለማጓተትና ቀጠሮዎችን ለማራዘም መጠቀሚያ መሣሪያዎች ናቸው።

በኢትዮጵያ ስለአለው ልዩ የቆንስላው ፍርድ፣ ስለፍትሕ ስርዓቱ፣ በፍትሕ መሣሪያነት ሁል ጊዜ ነጮችን ጥፋተኛ አድርጎ በመፈረጅና ውሳኔ በማሳለፍ በኩል ያለበትን ድክመት በተመለከተ በቂ ማስረጃ ያቀረብን ይመስለኛል። በኢትዮጵያ ፍትሕ የሚተገበርበት መንገድ በነጮችና በኢትዮጵያውያን መኻል ያለውን ውጥረት በማብረድ ፈንታ የሚያባብስና መጥፎ ስሜት በመፍጠር ላይ መሆኑን እስካሁን በቀረቡት ማስረጃዎች ግልጽ አድርገነዋል።

## የኢትዮጵያ የመከላከያ ኃይልና ጦርነት የማካሄድ አቅሙ

በኢትዮጵያ በነጮች ላይ የሚካሄደውን ጥላቻ በማስፋፋትና ሕዝቡንም በማነሳሳት ተግባር ላይ የተሰማራው የንጉሠ ነገሥቱ የክብር ዘበኛ ሠራዊት ነው። ፊታውራሪ ብሩ ለረጅም ጊዜ የዚህ ጦር አዛዥ ነበር። ከ1935 ጀምሮ ደግሞ ራስ ሙሉጌታ የጦሩ ዋና አዛዥና የጦር ሚኒስትር ነው። ስለዚህም

በካቢኔ ስብሰባዎች ላይ ይገኛል፤ እንዲሁም በሕገ መንግሥቱ ላይ በሰፈረው መሠረት ንጉሡ በማይኖርበት ጊዜ ከነሙሉ መብቱና ክብሩ ንጉሡን ይወክላል።

በዕዙ ስርም የኢትዮጵያ ጦር ሠራዊት በጠቅላላው ሲሰለፍ በትክክል ቁጥሩ ባይታወቅም ከሩብ ሚሊዮን አያልፍም። አራት የሚሆን ሬጂሜንት እግረኛ፤ ሁለት ስኳድሮን ፈረሰኛ፤ እና ጥቂት የከባድ መሣሪያ ቡድን ታጥቀውና ለብሰው በአውሮፓያኑ በኩል ተሰልፈው በተጠቀሱት የውጭ ዜጎች ወታደራዊ ሚሲዮኖች ሠልጥነዋል። እነዚህ የጦር አባላት በጣም ካረጁና ዘመን ከሻራቸው አንስቶ እስከ ዘመናዊ መሣሪያዎች የታጠቁ ሲሆን 250 የሚሆኑ አውቶማቲክ ጠመንጃዎች፣ ከኢጣልያ መንግሥት ለራስ መጠበቂያ ተብሎ የተቸረ አንድ ታንክ፤ ከአስሩ ስድስቱ የፈረንሳይ ስሪት የሆኑ ፖቴዝ ቦንብ ጣይ አውሮፕላኖች አሏቸው።

ኢትዮጵያውያን መሣሪያዎቻቸውን ለማደስና ዘመናዊ ለማድረግ፤ ያላቸውንም ክምችት ለማበራከት ሌት ተቀን እየጣሩ ነው። በስውር መሣሪያ ማስገባታቸውም የአደባባይ ምሥጢር ነው፤ የኢትዮጵያ መንግሥት በደላሎች የሚፈልገውን ለማግኘት እንደማይቸገር የተረጋገጠ በመሆኑ ማንኛውንም ነገር ለመደበቅና በምሥጢር ለማከናወን ችሎታ ካላቸው ደላሎች ጋር ባደረገው ውል መሠረት መሣሪያዎቹን ለማስገኘት በአዲስ አበባ ውል ፈጽሟል። መንግሥቱ "ለአይነት ያስፈልገኛል" ብሎ ያለ ክፍያ ያስመጣውን የተለያየ መሣሪያ ከገባ በኋላ "የቀረጥ ሕግን ሳይከተል ያለአግባብ የገባ ነው" በማለት በሐሰት ዴክሌራሲዮን የገባ መሆኑን እያወቀ ይወርሰዋል።

ለዚህ የሚሆነው ብቸኛ ማስረጃ በ1935 ጸደይ ወራት በሰሜን ኢትዮጵያ ግዛት በመቀሌ ጃፓን ሠራሽ የሆኑ መሣሪያዎች ተገኝተው ነበር፤ ሆኖም ግን መሣሪያዎች ከቶኪዮ ወደ ኢትዮጵያ በሽያጭ መሄድ አለመሄዳቸውን በተመለከተ አንዳችም መግለጫ አልተሰጠበትም።

በኢትዮጵያ እያንዳንዱ ነጻ ሰው፤ እንዲሁም የሐብታም አሽከር ሁሉ መሣሪያ አለው፤ በወገቡ ዙሪያም ጥይት የተሞላበት ዝናር ይታጠቃል፤ በጦር ጊዜም ተጠባባቂው ሠራዊት ስለሚጠራ የሠራዊቱ ብዛት ወደ 750,000 እንደሚያድግ ምንም አያጠራጥርም። ሠራዊቱ የሚከተው ከሁሉም ግዛት በመሆኑ በውጊያ ጊዜ እንደ መሣሪያዎች መደበላለቅ ሁሉ የተዛመደ ሂደት አይኖረውም።

ኢትዮጵያውያን በተፈጥሯቸው ጦር ወዳዶችና ጀግኖች ናቸው። ነገር ግን ጥቂቶች ብቻ ናቸው የመሣሪያ አጠቃቀም የሚያውቁና በሚያስፈልግበት ቦታና ጊዜ ሊጠቀሙበት የሚችሉት።

በኢትዮጵያ ውስጥ አብዛኛዎቹ ሰዎች ፎቶግራፍ የሚነሱት አይናቸውን ጨፍነው ነው። በእርግጠኝነት 3/4ኛ የሚሆኑት ኢትዮጵያዊያን የሚተኩሱት ሳያነጣጥሩ በነሲብ ነው። ድምጹ ከፍተኛ በሆነ መጠንና የሰዉም ጩኸት በበዛ ቁጥር ደሥታቸው መጠን ያጣና የተያዘው ጥይት ሁሉ በእሩምታ ተተኩሶ ያልቃል።

ኢትዮጵያን እንደነገሩ ጥይት ያመርታሉ ተብሎ ቢታሰብም ኢትዮጵያ ላይ ጦር ቢሰነዘር፣ ባህር አልባ ሀገር እንደመሆኗ፣ ከውጭ ከሚገኘው አቅርቦት ጋር ስለምትለያይ ጥይት አጠቃቀማቸው ላይ ጥንቃቄ ሊያደርጉ ይገባል። የነፍጥ አጠቃቀም ስልጠና አለመኖር የኢትዮጵያን ጦር ሰንካላ ያደርገዋል።

አውሮፓውያን ወታደሮች የዓየሩን ጠባይ ስለማይቋቋሙት፣ የውሃው እጥረት፣ የተመጣጣነ ምግብ አለመኖር ጉዟቸውን አድካሚና ረጂም ስለሚያደርግባቸው፣ ልብሳቸው ስለማይሟላ፣ እንዲሁም የሀገሪቱ አቀማመጥ ከፍና ዝቅ ስለሚል ኢትዮጵያዊያን ወታደሮች የበላይነት ይኖራቸዋል። የውጭ ወታደሮች ከበረሃውና ከተራራው የተነሳ በጉዞ የሚሸፍኑት ርቀት መጠነኛ ነው። የወረርሽኝ በሽታ ለሰውም ሆነ ለእንስሣት አደገኛ ነው።

ታንኮችንና ከባድ መሣሪያዎችን በአሸዋማና በአልሠለጠነ መንገድ ላይ ለማጓጓዝ እንደሞሮኮ እልህ አስጨራሽና አድካሚ ይሆናል። የዐየር ጥቃትም ቢሆን የተሰባሰቡ ወታደሮችን ለመፍጀት፣ አለያም ለማስፈራሪያነት ካልሆነ በቀር የተወላጆችን ደሳሳ ጎጆ ቤቶች በቦምብ ማጥፋቱ ጠቀሜታው አነስተኛ ነው።

እነዚህን ያልተለመዱ ሁኔታዎች ግምት ውስጥ በማስገባት በኢትዮጵያ ላይ ዘመቻ ለማድረግ ያለው የባለሙያዎች እይታ በተለየ ሁኔታ የሚገመት ሆኖ ይገኛል። በእርግጥኝነት መናገር የሚቻለው፣ በኢትዮጵያ ድንበሮች ላይ በችኮላ ወደፊት ለመግፋት መሞከር አደገኛ መሆኑንና ውጤታማ ለመሆን በጥንቃቄና በትዕግስት ቀስ በቀስ ለመዝለቅ ማቀድ፣ ድል ለተደረጉት አካባቢዎች አስፈላጊውን መገናኛ በማስተካከል፣ የባቡር ሐዲድ በመዘርጋት፣ ድልድዮችን በመገንባት፣ የቴሌፎን መስመር በመዘርጋት እና የውሃ ቧንቧዎችን በመትከል ከቅኝ ግዛቱ ባሕረገብ መሬት ጋር ግንኙነት መገንባት አስፈላጊ ነው።

በሀገሪቱ ዘልቆ ለመግባት በሩን መክፈት ቢያስፈልግም በወታደራዊ ኃይልና በተፋጠነ ሂደት የሚሳካ አይሆንም፣ ይልቁንም ድሉ የሚረጋገጠው በሀገሪቱ ከሚገኙ የጠረፍ ነዋሪዎች ጋር ወዳጃዊ ግንኙነት በመመሥረትና ያንንም በማጠናከር፣ ልማትንና ዕድገትን በማረጋገጥ፣ ከሀገሩ ባላባቶች የጭካኔና አረመኔያዊ አገዛዝ የሚላቀቁበትን ተሥፋ በማሳየት፣ የሹመት ተሥፋ በመስጠትና በጊዜያዊ ጥቅም በመያዝ ብቻ ነው።

መታሰብና መታወስ ያለበት ጉዳይ ኢትዮጵያ ውስጥ የሚኖሩት አብዛኛዎቹ ሕዝቦች ተጨቋኞች ናቸው፣ ጨቋኞቹ ገዢዎች ደግሞ አማሮች ናቸው። በሁሉም አቅጣጫ የሚሰማው "በኢትዮጵያ ጦርነት ይኖራል" የሚለው ነው። ስለዚህ ጣልያን ሀገሪቱን ንብረቷ ለማድረግ ሰውና መሣሪያ ይኖራታል፣ ጉዳዩ ቦስኒያንና ሄርዞጎቪናን ከመያዝ ያላነሰ ነው። ሀገሪቱን ቅኝ ማድረግም የሀገሪቱን መረጋጋት ያረጋግጣል፣ ለአውሮፓውያን ክፍት በማድረግም ለአውሮፓ ሥልጣኔና ልማት እንዲነሳሱ ያደርጋል። የቅርብ ታሪክ በአስተማማኝ እንዳረጋገጠው በአዲስ አበባ የሚገኘው መንግሥት ይህንን ለማድረግ ፈቃዱም ፍላጎቱም የለውም። አዋጆቹና የገባው ቃልም በግዛቱ ከታየው እውነታ በተጻራሪው በመሆኑ በኢትዮጵያዊው መልእክተኛ አቶ ተክለሐዋርያት አማካይነት የቀረበው ሰብአዊ መብቶችን የሚመለከተው አቤቱታ ከግብዝነት ያለፈ አይሆንም።

በመስከረም 11/1935 ለዓለም መንግሥታት ማኅበር ባሰማው ንግግር ላይ እንደገለጸው የአፍሪካን አፈር በሰብአዊ ወንድሞቻቸው ደም ማቅላትን መታገስ ግብዝነት ነው። ኢትዮጵያውያን እስካሁን ድረስ በቂ ደማቸውን አፍስሰዋል፤ ስለዚህ በኢትዮጵያ ያለውን የስርዓት አልበኝነት ሁኔታ ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ለፍጻሜ ማብቃት ያስፈልጋል።

በአግባቡ ለመረዳት ያሰበና ስለጉዳዩ ጥልቅ እውቀት ያለው ሰው "ኢትዮጵያ በጦርነት ድል አትደረግም፤ በሹመት፣ በጥቅምና በመሳሰሉት ትገዛለች እንጂ" የሚለውን የብልሁን የፈረንሳይ ሚኒስትር የክሎቡኮውስኪን ንግግር ሊያስታውስ ግድ ነው።

## ድንበር የለሹ የኃያላን ምድር

አውሮፓውያን በኢትዮጵያ ስላለው ሁኔታ ትክክለኛ ግንዛቤ ለማግኘት እና ነጮች "ይቻላል ብለው ባላሰቡት ነገር ላይ እየተንፈራገጡ ነው" የሚለው አስተሳሰብ ገና ያላለቀ አመለካከት ነው።

ጥቁሮች ምንግዜም ቢሆን ነጩን እንደ አስተማሪ፤ እንደ ጋሻ መከታቸው፤ ቢያንስ እንደ በላያቸው እንዳይመለከቱ ተደርጓል። ይህ ደግሞ በተለይ አደገኛ የሆነ ቁንጽል ትምህርት በአውሮፓ ዋና ከተሞች እና ችግር ባለበት ለዘብተኛ ትምህርት ቤት በሚደርስባቸው የልዩነት አመለካከት ወጣት ኢትዮጵያውያን በሚባሉት ላይ በእርግጥም እውነት ነው። እነዚህም ወደሀገራቸው ይመለሱና በነጮች ላይ ጥላቻና ጠብ ያጭራሉ።[12]

እነዚህ ወጣት ዜጎች በአብዛኛው ዕድገታቸው ፈረንሳይ ውስጥ በመሆኑ፤ የኢትዮጵያ መንግሥት ስላለው ፖሊሲ በትውውቃቸው አጋጣሚ በሚያገኟቸው ሰዎች ተሰሚነት እያገኙ ነው። ሊጤን የሚገባው ቁምነገር የኢትዮጵያው የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የብላቴን ጌታ ሕሩይ ልጅ ጆርጅ ህሩይ የዚህ የኢትዮጵያ ወጣቶች ማኅበር ሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ ሰብሳቢ መሆኑ ነው።

ማኅበሩ የፖስታና ቴሌግራፍ ወጣት ባለስልጣናትንም ያካተተ መሆኑ ሊጤን ይገባል። ዓላማቸው አድርገው የተነሱትም በሁሉም የመንግሥት መሥሪያ ቤቶች ውስጥ ኃላፊነቱንና አመራሩን ወጣቶች እንዲይዙት ለማድረግና ቀስ በቀስም ለብዙ ዓመታተ ያገለገሉትንና ለአውሮፓውያን ወዳጅ የሆኑትን አበው ባለሥልጣናት ማስወገድ ነው። ይሁንና እነዚህ ወጣት ኢትዮጵያውያን

12 የአውሮውያንን ቅንነት በወጣት ኢትዮጵያውያን እንቅስቃሴ ውስጥ ለማስረጽ ምን ያህል አስቸጋሪ እንደሆነ በሰኔ 1935 በፈረንሳይ ይግባኝ ችሎት የቀረበውን አጋጣሚ ማየትና ማገናዘብ ይቻላል። ጉዳዩ የኢትዮጵያው ንጉሥ የአጎት ልጅ ከሆነውና በጄኔቭ ሕግ በመማር ላይ ከነበረው ልዑል አርዓያ ኃይለሥላሴ ጋር የተያያዘ ነው። ይኸው የንጉሡ ዘመድ "ጃኒላ ጋላየቲ" ከተባለችው የ"ትሪቢዩን ደ ኦርየንት"ጋዜጣ ዳይሬክተር ልጅ ጋር ይተዋወቃል። ልዑሉ ለፍቅር ያቀረበውን ጥያቄ ለመቀበል ፈቃደኛ ያልሆነችውን ልጃገረድ በአደባባይ አፍንጫዋን ነክሶ በመቁረጥ ዋጠው። በመጀመሪያ ጉዳዩ የቀረበለት ፍርድ ቤት ያስተላለፈው ቀላል ቅጣት በይግባኝ ወደ አንድ ዓመት እስር ተለወጠ። ይህ አጋጣሚ የተጠቀሰበት ምክንያት በፖለቲካ አመለካከት ሁኔታው እንዴት እንደተካሄደ ለማሳየት ነው።

ለበታዎቹ ብቃት ስለሌላቸው፣ ባሕርያቸውም አስቸጋሪ በመሆኑ፣ በተደጋጋሚ ጥያቄያቸው ተቀባይነት ስለሚያጣና ሌላም ችግር ስለሚያስከትልባቸው፣ ይህንን ሰበብ በማድረግ በአውሮፓውያን ላይ ጥላቻ ይነዛሉ። ለምሳሌ ስሙን ብቻ ከመጻፍ የማያልፍና ምንም ችሎታ የሌለው ከፊል መሐይም የፖስታ ሚኒስትር ሆኖ በወር 500 ታህለር ሲከፈለው፣ አማርኛ፣ ግሪክ እና አረብኛ አቀላጥፈው የሚናገሩትና የሚጽፉት ምሑራን ግን በኢትዮጵያ ባለው ሁኔታ የሚከፈላቸው ከ15 ታህለር አንስቶ ነው።

ሌላውና እረፍት የሚነሳው አዲስ አበባ አቅራቢያ በሚገኘው ሰፈራ ያለው "የአሜሪካን ሆስፒታል" ሰራተኞች ግልጽ መግለጫ ነው። ድርጅቱ ኢትዮጵያውያንን ለመርዳት ተብሎ የተቋቋመ በመሆኑ አውሮፓውያን አገልግሎት የሚያገኙት እንደ ውለታ ነው። በአፍሪካ ጥቁሮች ህክምና የሚያገኙትና አስፈላጊው እንክብካቤ የሚደረግላቸው የነጮችን ጥቅም ባላካተተ መልኩ በመሆኑ ነጮች ገደል ቢገቡ ግድ ያለው ሰው አይኖርም።

በኢትዮጵያ መንግሥት ብዙ ሙከራ እንደተደረገ ይነገራል። እውነቱ ግን ይህ መንግሥት በጣም መራር የሆኑትንና አስከፊ የሚባሉትን ጎጂ ድርጊቶች እንኳ ገና አላስወገደም። የሞቱ እንስሳት ጥንብ ለጅቦችና ለውሾች መራኮቻ ሆኖ በአዲስ አበባ አውራ ጎዳኖዎች ላይ ቀን በቀን ተዘርግቶ ይውላል። በከተማው መኻል ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን አጠገብ በርካታ አካል ጉዳተኞች በአስከፊው የቁምጥና በሽታ እየተሰቃዩ ናቸው፣ የገዘሆኔ እብጠት ተጠቂዎችም በግማሽ የሞቱ ያህል ሆነው፣ ሁሉም በዝንብ ተወርረው በየመንገዱ ላይ በመደርደር እጃቸውን ዘርግተው አላፊ አግዳሚውን ምጽዋት ይጠይቃሉ። የቁምጥና ተጠቂዎችም በከፊል ፊታቸውን ሸፍነውና መምጣታቸውን ለማሳወቅ በአንገታቸው ላይ ደወል አንጠልጥለው ይለምናሉ፣ ሲያስፈልግም እንዴት ከፍ ያለ ምጽዋት ማግኘት እንደሚችሉ ያውቃሉና ሁኔታቸውን እንደማስገደጃ ይጠቀሙበታል።

ከአካባቢ ጽዳት አኳያ በዝቅተኛ የኑሮ ደረጃ ውስጥ ያሉ ኢትዮጵያውያን የሙት ወገኖቻቸውን አስከሬን የሚያስወግዱበት ሁኔታ እጅግ የከፋ ነው። እነዚህ ቤተሰቦች የመቃብር ጉድጓድ በአግባቡ ቆፍሮ ለመቅበር እንኳ ሰነፎች ናቸው። በድኑን ወደ ቤተክርስቲያን ቅጥር ግቢ ያደርሱና ጥቂት አሸዋ አለያም አፈር አልብሰው ድንጋይ ጭነውበት ይተዉታል። በሙቀቱ ኃይለኛ ቃጠሎ የተነሳ ቶሎ ይበሰብስና ወዲያው አደገኛ ባክቴርያዎችን ይፈለፍላል። ይህ ደግሞ በማደግ ላይ ላለች ከተማ አደጋው የከፋ ነውና በአውሮፓውያን ድጋፍና ምክር ከዚህ ተግባር መገላገል ይገባቸዋል፣ መንግሥትም ለቀላሉ የትራፊክ ጉዳይ ከሚሰጠው ትኩረት ይበልጥ ለዚህ አሳሳቢና አደገኛ ሁኔታ ሊጨነቅ ይገባዋል።

ንጽህናንና ጤንነትን በመከታተል የሚሠራው መሥሪያ ቤት በታህሳስ 23/1933 በታተመው "Les Thermes d'Addis Ababa" በገጽ 5 ዕትም ቁ. 77 "Ethiopic Commercial" ባቀረበው ዘገባ ላይ በግልጽ አትቷል። እኔም የመጸዳጃ ቤቶችንና የቁም ሳጥኖችን እንደ በቅሎ ጉሮኖ መጠቀሚያ አውለውት

ተመልክቻለሁ። ንጽህናቸው ያልተጠበቀ አገልጋዮች ለእንግዶች በተዘጋጀ አልጋ ላይ ይጋደማሉ፤ ሌሎች ማመን የሚያስቸግሩ ድርጊቶችንም ይፈጽማሉ።

በአውሮፓዊያን ጋዜጦች ላይ ስለ ኢትዮጳያ መጥፎ ሁኔታዎች ለምን እንደማይጻፍና በአሸበረቁ ቃላት የሚያምሩ ሐተታዎች ብቻ ለምን እንደሚወጡ አይገባኝም። አሁን በኢትዮጵያ ጉዳይ ላይ አውሮፓውያን ጣልቃ ገብነታቸው እንደሚያስፈልግ የሠለጠነውን ዓለም አመለካከት ማስተካከል ያስፈልጋል።

ኃላፊነቱን በሚገባ የሚገነዘበው "ኦሰርቫቶር ሮማኖ" የተባለው የኅትመት ውጤት እንኳ በእውነት በጣም ቀና በሆነ አመለካከትና ትዕግስት በሰፈነበት ሁኔታ ስለ ሃይማኖታዊው ስርዓትና ኋላ ቀር ስለሆነው የአገልጋዮቹ ሁኔታ ጽሑፍ አውጥቷል።ያንን ንጽህና የጎደለውንና ማይማን የሆኑት የጉባኤ አባላት ክምችት የሚያቀርቡትን፤ ከዚያ ኋላ ቀር ከሆነው ዳንሳቸው ጋር አረመኔያዊነትና የመናፍስት አምልኮ ቅልቅል የሆነውን ባህል እንዴት "የሃይማኖታዊ ሕብረተሰብ ባህላዊ ሀብት" ተብሎ ሊጠቀስ ይችላል።

ኢትዮጵያውያን ለማንኛውም የነጮች ውጥን ትዕግስት የላቸውም። ሰንካላ እውቀታቸው ስለሚያመዝን ፈረንጅ የሚሠራውን ማንኛውንም ቀና ድርጊት የእኩይ ምንጭ እና ለሐበሻ መንግሥት አደጋ ነው ብለው ያምናሉ "ሐበሻ" ሲሉም የኢትዮጵያን አገዛዝ ለማለት ነው።

አንድ አውሮፓዊ ትዕግስት የሚያስጨርስ ሁኔታ ላሳየው ፖሊስ፣ ወይም የቀረጥ ተቆጣጣሪ፣ ወይም ለማንኛውም የሀገሬው ባለሥልጣን ተቃውሞውን ለማሳየት ቢሞክር ጩኸቱ፣ ግርግሩና ወከባው ይጧጧፍና "ነጩ የሐበሻን መንግሥት ተቃወመ" የሚል ክስ ይመሠረትበታል። በሌላ ጎኑ አንድ የኢትዮጵያ ባለሥልጣን ግፍ ቢፈጽም "የሐበሻ መንግሥት" የሚለው እንደጉም በንኖ ይጠፉና መንግሥት ለድርጊቱ አንዳችም ኃላፊነት አይወስድም።

ይህ ደግሞ በፖለቲካው ምኅዳር ብቻ ሳይሆን በዕለት ተዕለት ተግባርም የሚታይ ነው። አህያ በመኪና ቢገጭ ወዲያው አቧራ ያጨሳሉ። ነገር ግን አንድ ነጭ በመኪና በሚያልፍበት ወቅት መንገዱ በከብቶች ቢዘጋ፤ ባለቤቱ በአካባቢው አይታይም። ከብቶቹ እስኪያልፉ በመጠበቅ ፋንታ በላያቸው ላይ ለመንዳት የሞከረ ወይም ጥሩምባውን ያስጮኸ ነጭ እሱን አያድርገኝ! በጥቂት ደቂቃዎች ውስጥ ባሕል መሠረት ግርፋት ሊደርስበት ይችላል።

በማዕከላዊው የሀገሪቱ ክፍልም ተወላጆቹ በተቻላቸው መጠን የነጮችን ተግባር በመላ ለማጥላላት ይጥራሉ። በ1933 የንጉሠ ነገሥቱን ፓስፖርት የያዙ የአሜሪካ የመሬት ቅሪት ተመራማሪዎች ቡድን አባላት በተለያዩ መንደሮች ውስጥ የራስ ቅሎችን ለመለካት ሲሞክሩ በመሣሪያ በመታገዝ ምርምሩን እንዳያካሂዱ ተደርገዋል።

# ቀለማሞቹ በመላው ዓለም

ቀለማም ሰዎችን በድንገት ወደ ከፍተኛ ደረጃ ባሕል ለማሸጋገር የሚደረግ ማንኛውም ጥረት እንደሚከሽፍ የተረጋገጠ ነው። ይህንን ከማንም በበለጠ የሚያውቁት የክርስቲያን ሚሲዮናውያን ናቸው። ምንም አይነት ትምህርትና የትምህርት ቤት ሥልጠና ቀለማሞቹን ሕዝቦች እንደማይለውጣቸውና ነጮች የያዙትን ቦታ ተክተው መሥራት እንደማይችሉ የዓለም አቀፍ ልምድ ያረጋገጠው እውነታ ነው።

በ1933 የቤልጂጋውያን ኮንጎ ገዢ ለነበረው ጄኔራል ቲልኬንስ ጥቁሩ ጆሴፍ ቱካሪ የጻፈው ደብዳቤ ብዙ ሁከት አስነስቶ ነበር። በደብዳቤው ላይ ያነሳው ጉዳይ በቂ ትምህርት ተከታትሎ ችሎታ ያለው በመሆኑ ክብርና ምደባ እንዲሰጠው ነበር። ለዚህ ጥያቄው ምላሹ “መልካሙ ባርያ” (Le Bon ne’gre) በሚል ርእስ “ኔፕቱን” በተባለ ጋዜጣ ላይ ተገልጿል (ብራስልስ ጥቅምት 4/1933)። ጸሐፊው ጥቁሩን መብት ጠያቂ የምትሃተኛ ፋኖስ ካላየችው ዝንጀሮ ጋር በማመዛዘን “ማየቱን አይቷል ግን ልዩነት አላሳየም!” በማለት ነበር ያስረዳው።

የተሻለ ብቃት ያላቸው የአገሬው ሰዎች ነጻ የመውጣት ጽኑ ምኞታቸው ግምት ውስጥ አልገባላቸውም፤ የዘወትር ድርጊታቸው እንደሚያመለክተው በአውሮፓ የተማሩትን የራሳቸውን ዜጎች ዝቅ አድርገው ከመመልከታቸውም በላይ ቀልበ ቢስ አድርገው ስለሚያስቧቸው ለራሳቸውም ይሁን ለሀገራቸው “ይህ ነው” የሚባል ዕርዳታም ሆነ እድገት ያመጡልናል ብለው አያምኑም።

ባሕሎቻቸውንና ልምዶቻቸውን ይንቃሉ ብለውም ይወነጅሏቸዋል፤ ከነጮች ጋር ለግል ጥቅማቸው ሲሉ ምሥጢራዊ አንድነት ፈጥረዋል ብለውም ይጠረጥሯቸዋል።

በአፍሪካ ውስጥ ስርዓትና የደኅንነት ዋስትናን ለማረጋገጥ በአውሮፓውያን ከመተዳደር የበለጠ ማረጋገጫ የለም። ለሀገሬው ሰዎችም ልማትና እድገት ማረጋገጫው ይኸው ነው። ይህንን ግዛት በአግባቡ መሥርቶ ማጠናከር ማለት ለዓለም ሰላም አስተዋጽኦ ማድረግ ነው። በመላው የአፍሪካ ክፍሎች የሚታየው የጥቁሮች መነሳሳት፤ ወሳኝና አስቸኳይ ውሳኔን ይጠይቃል።

በ1933 የበጋው ወቅት የኮንጎ ቅኝ ገዢ የሆነው የቤልጂግ መንግሥት የአንዮታስ ንጉሥ የነበረውን እምባኩን በሰንሰለት አስሮ ለወራት አከረመው። ሕዝቦቹም “አጠቃላይ የነጭን ዘር እንዲደመስሱ ንጉሡ ትእዛዝ ሰጥቶ ነበር” ምንም እንኳ እግር ተወርች ቢታሰርም “ነብሮቹ” ከሚላቸው ሰዎች ጋር ለመገናኘት በቅቶ፤ በአውሮፓውያን ላይ ርኅራሄ የሌለው ጭፍጨፋ አካሄዱ።

የእንግሊዝ ዘውድ ቅኝ በሆነችው ኬንያ፤ መሠረቱ ሞልታ የሆነው ገበሬ አሌክሳንደር ሶሚኒ እና ባለቤቱ በሰኔ 15/1934 በሉምብዋ ጥቁሮች ጥቃት ተሰነዘረባቸው። በደረሰበት ጉዳት ሰውዬው በናይሮቢ ሆስፒታል በህክምና ላይ እያለ ሕይወቱ አለፈች። ሐምሌ 19/1934 ላይ ታይም እንደዘገበው፤

በኬንያ የሚገኘው "የምስራቅ አፍሪካ ሴቶች ማኅበር" አባላት ለገዢው በላኩት አቤቱታ "ተወላጆቹን ለመቆጣጠር ጥብቅ እርምጃ እንዲወሰድና የሀገሬው ጥቁሮች ነጮችን እንዲያከብሩ፣ ሕግና ስርዓትም እንዲከበር፣ በመታያት ላይ ያለው ወንጀል ጉዳቱ አስከፊ ከመሆኑ በፊት መቆሚያ እንዲደረግለት" አሳስበዋል።

በነጻነት የሚጽፈው ኤሚል ሉድዊግ "በአፍሪካ በየጊዜው ጥቁሮች በነጮች ሴቶች ላይ የሚፈጽሙት ወንጀል እየጨመረ የሚሄድበት ምክንያት በወንጀል ተሳታፊዎች ላይ የሚተላለፈው ቅጣት በጣም ቀላል በመሆኑ ነው" በማለት አስተያየቱን አስፍሯል።

የቤችዋናላንድ ጎሣ መሪ ቼኬኬዲ የእንግሊዝ ዜጋ የሆነውን ማክ ኢንቶሽን ችሎት ላይ አስቀርቦ ስላስገረፈው የእንግሊዝ አድሚራል ኢቫንስ ጉዳዩን ለመመርመር ተወክሎ ነበር። በወቅቱ ከፍተኛው ኮሚሽነርና ገዢው ሰር ሁበርት ስታንሌይ ፈቃድ ላይ ነበሩና ይህን ከፍተኛ የግፍ ድርጊት አምርሮ አውግዞታል።

ድርጊቱን በተመለከተ በፈረንሳይኛ መጽሔት "Je suis par tout" ላይ (ፓሪስ ጥቅምት 7 1933) "ሆነም ቀረ ደንብ ሲተላለፉ በለንደንም ልጆች ይገረፋሉ" ብሎ ነበር። ጨርሶ ነጥቡን የሳተ አባባል። አንድ የእንግሊዝ ዜጋ በቅኝ ተገዢ አፍሪካዊ ችሎት ላይ የተፈጸመበትን የግርፋት ተግባር ተማሪዎችን ከጥፋት ለማረቅ በመምህራን ከሚደረግ ግርፋት ጋር ማወዳደሩ በጣም አሳፋሪ ነው።

በቅርቡ ከዚህ ዓለም በሞት የተለየው መልካሙ የአፍሪካ ዳኛ ፈረንሳዊው ማርሻል ላዩቴይ ጥቁሮችን ከሚያስፈልገው በላይ መታገስ የሚያስከትለውን ከባድ አደጋ በሚገባ ተረድቶ ነበር። ጄኔራል ዌይንጋድ በርካታ ቁጥር ያላቸውን አፍሪካውያን ወታደሮች በፈረንሳይ ለመመደብ ሲያቅድ፣ ድርጊቱ ከፍተኛ ስህተት መሆኑን አስገንዝቧል ("ማቲን ታህሳስ 3/1933)። ለመላው የምዕራብ አውሮፓ ሥልጣኔ ይኸ ድርጊት የሚያስከትለውን አደጋም ዘርዝሯል።

በመላው ሰሜን አፍሪካ በመካሄድ ላይ ያለው ፀረ-ፈረንሳይ አመጽና ጥላቻ የሚያመለክተው የማርሻሉ አባባል ትክክል መሆኑን ነው። ከፈረንሳይ ዜጎች እኩል ለጥቁሮች መብት የመስጠቱ መዘዝ ውጤቱ በፈረንሳይ ውስጥ በመረረ ሁኔታ እየታየ ነው። ከምንም በላይ ከደማስቆና ከካይሮ የተወለደው አፍቅሮተ እስልምና ቅስቀሳ ሲሆን፣ በአውሮፓ ቅኝ አገሮች ሁሉ የሚገኙትን እስላሞች የሚያስተሳስርና የሚያነሳሳ ጥላቻን በመንዛት በነጭ ዘር ላይ አመጽ እንዲካሄድና ጥላቻውም በበለጠ እንዲነግሥ የሚያደርግ ነው። "የጥቁሮች ሕብረት በጭቆናና በኢምፔሪያሊዝም ላይ" ከ1927 አንስቶ ጉባኤ በማካሄድ ላይ ይገኛል። የተግባር ኮሚቴው በመላው ዓለም ከአረብ ጠረፍ /ቱኒዝያ/ አንስቶ እስከ በርሊን የማታ ክበብ ሳክስፎን ተጫዋች ድረስ በመዝለቅ፣ ሁሉንም ዘርና ደረጃ በማካተት ከነጭ ጋር ለሚደረገው ወሳኝና የመጨረሻ ፍልሚያ በዝግጅት ላይ ነው።

ከዚህ እንቅስቃሴ በተጓዳኝ አፍቃሬ ኤኽያውያን ፕሮፓጋንዳም አለ። በነሀሴ 1934 ሺምቦን-ሬንጎ የዜና አገልግሎት "ታላቁን የኤኽያ ማስተባበሪያ

ሕብረት" በቶኪዮ መመሥረቱን ዘግቧል። በሕብረቱ ውስጥ ታላላቅ የፖለቲካና የንግድ ባለቤቶች ከጃፓን፣ ከማንቹሪያ እና ሞንጎሊያ በአባልነት ተካትተዋል። በ1905 ከተካሄደው የሩሶ-ጃፓን ጦርነት ወዲህ በፈረንሳይ ኢንዶ ቻይና ያሉት የጃፓን ሰላዮች መጪውን የጃፓን ድል በማስመልከት በራሪ ወረቀቶችንና እና ፎቶተግራፎችን በመበተን፣ ወደፊትም በአውሮፓውያን ሰርጎ ገቦች ላይ የቲና አስተናጋጆች ስለሚወስዱት እርምጃ አስጠንቅቀዋል።

"ኤዥያ ለኤዥያውያን" የሚለው ጠብ አጫሪ የጃፓን መፈክር በ1934 በጋ ወራት በባቫሪያ የደች ምሥራቅ ኢንዲስና በጃፓን መካከል በተካሄደው ድርድር ላይ ውጤቱ ታይቷል። በፖለቲካዊው መዝገብ ላይ የማያጠራጥረው የይገባኛል ጥያቄ በታዋቂው ባሮን ታናካ ለጃፓን ንጉሥ በተላከው ደብዳቤ ላይ የተጠቆመው ፍላጎት "ጃፓን በአውሮፓና በአሜሪካ ላይ ጀርባዋን እንድታዞርና የቀለማም ዘሮችን መሪነት እንድትይዝ እና በኤዥያ ውስጥ የበላይነቷን እንድታረጋግጥ" የሚለው ራዕይ በሁሉም ቀለማም ሰዎች ቅኝ አገሮች ሥር እየሰደደ ነው።

ለ"ታይምስ" ሎርድ ሎቲያን በየካቲት 1935 በጻፈው ግልጽ ደብዳቤ "ጃፓን ክርክር የማያስፈልገው ሁኔታ ለዓለም ለማቅረብ እቅድ አላት፣ ቻይና የዓለም ማኅበር አባልነቷን እድትሰርዝ የአውሮፓውያንንና የአሜሪካን አማካሪነት በመሰረዝ ከጃፓን ጋር የምስራቅ ኤዥያ አንድነትን እንድትቀላቀል ጠይቋል። ይህን በማድረግም በነጮች የተያዘውን የበላይነት ለማሸነፍና አመቺ ሁኔታ ለመፍጠር ከአባልነት የመውጣት ጥያቄ ማቅረቡ ትርጉሙ ጠቃሚ ነው" ይላል።

ብዙ ጊዜ እንዲህ አይነቱ አመቺ ሁኔታ አይደገምም። የቀለማም ሰዎች በጭቆናና በግፍ ላይ ሕብረት መፍጠር ኑሯቸውን አደጋ ላይ የሚጥል መሆኑን የምዕራቡ ዓለም መረዳት አለበት። ቀለማሞች በምሬት የነጮችን በደል መቋቋም ስለሚጀምሩ ከአደጋው በፊት ምዕራባውያን መፍትሔውን መሻት ምርጫቸው ሊሆን ይገባል። በምስራቅ ኤዥያም ሆነ በአፍሪካ ተወላጆች ኃይላቸውን በማጠናከር የነጮችን የበላይነት አሽቀንጥረው ለመጣል ተዘጋጅተዋል። ይህም ከኢትዮጵያ ይጀምራል፣ አዲሱ "ንቃ" የኢትዮጵያ እንቅስቃሴ በአፍሪካ ያሉትን ቀለማም ሰዎች በማስተባበር ላይ ነው። ጊዜ ባለፈ ቁጥር ማንኛውም ነገር ግልጽ እየሆነ መጥቷል፦ እንደፖለቲካ ሕብረት በኢትዮጵያና በጃፓን መካከል የኤኮኖሚ ትብብር፣ በኢትዮጵያና በግብጽ መካከል የፍላጎት መተሳሰር፣ ግብጽ ያላት የተትረፈረፈ የተማረ የሰው ሃይል ካላቸው ሃይማኖታዊ አንድነት የተነሳ ወጣቱን ትውልድ(1) ለማስተማርና ለማሠልጠን መልካም አጋጣሚ ነው። በአሜሪካ ባሉት ጥቁር አሜሪካውያን ዘንድ በጣም እየተሠራበት ያለው የኢትዮጵያ የፖለቲካ እንቅስቃሴ ጉዳይ፣ በኢትዮጵያ ጦር ውስጥ በፈቃደኝነት ለማገልገል እስከመወሰንና አውሮፕላንም እስከመቸር ደርሷል።

የኢትዮጵያና ግብጽ ማኅበረሰብ በዓባይ ላይ የኤኮኖሚ ልማት ለማከናወን የሚያስችል ግድብ ለመሥራት ስምምነት ሊደርሱ ነው። የዚህ ግንኙነትና ጥምረት አስተባባሪ በኢትዮጵያ ጵጵስናውን የሚያካሂደው ግብጻዊው አቡነ

ቁርሎስ ነው። በኢትዮጵያና በግብጽ መኻል የተፈጠረውን ስምምነት፤ የተደረሰበትን ደረጃ፤ ይዘቱንና ያካተታቸውን ውሎች በተመለከተ ጋዜጠኛው ዴቺዮ ዎሊንስኪ በሊበርቴ ጋዜጣ ላይ በ1934 መግቢያ በዝርዝር አስፍሮታል።

የጃፓን ሽብርተኛ ድርጅት "ሬሄይ ኡቺዳ" (ጥቁሩ ድራጎን) ለኢጣልያ መንግሥት ከፍተኛ ባለሥልጣን የማስፈራሪያ ቴሌግራም ሲልክ ነበር። ማህትማ ጋንዲ ለኢትዮጵያ የሚውል የዕርዳታ ገንዘብ በህንድ በማሰባሰብ ላይ ነው፤ እንዲሁም የሂንዱ ተወካይ ጊሪ ድምጽ በማሰባሰብ ጣልያን በቀለማም ሰዎች ላይ ስለምትፈጽመው ተግባር በፓርላማ ውግዘት እንዲደረግ በመጣር ላይ ነው።

በኢትዮጵያ ላይ ስለሚታሰበውና ስለሚያስከትለው አደጋ በእንግሊዝ በአጣዳፊ አማራጭነት መቅረቡ፤ በኢትዮጵያ ጠረፍ ላይ የሚገኙት የተለያዩ የአውሮፓ አገሮች ቅኝ ተገዢዎች አተያይ እንደውጭ ዜጎች ልክፍት[13] ይታያል።

# ማጠቃለያ

ይህ አዝማሚያ እየተዛመተ እንዳይሄድ የሰለጠኑት አገሮች ተቀናጅተው የጋራ እርምጃ የሚወስዱበት ጊዜው አሁን ነው። በአዲስ አበባ ያለው የኢትዮጵያ መንግሥት ደንብና ሥርዓት እንዲከበር፣ በአፍሪካ ባሉ የቅኝ ግዛት ኃይሎች ላይ የሚሠራውን ደባ፤ አስከፊና ሕገወጥ ድርጊት ለማስከበር ምንም ያህል ፈቃደኛ ቢሆንም ሊያደርገው ግን አይችልም።

በአጠቃላይ ሀገሪቱ ላይ የሕግ አስፈጻሚነት ሥልጣን ስለሌለው፤ እና ተመጣጣኝና በቂ እውቅናም ስለማይሰጠው፤ የአውሮፓ አገሮች ሁኔታ በድንገተኛ አደጋ ውስጥ ወድቋል። በዚህ ምክንያት በድንገተኛው የንቅናቄ ንዳድ የመጨረሻውን የሥልጣን ትርጉም ማጣቱ እየተቃረበ ነው። ስለዚህ መደረግ ያለበት በድንበር ላይ ያሉትን በሮች ከመንግሥቱ ጋር በመስማማት ማስከፈት። በዚህ መሠረት አቅጣጫውን ማስቀየርና በመጨረሻው ሰዓት ሁኔታውን ለአውሮፓውያን ማመቻቸት ይቻላል።[14]

የሊቢያ ገዢ ሆኖ በተሾመበት ጊዜ ጣልያናዊው የዓየር ኃይል ማርሻል ባልቦ የሚከተለውን ተናግሮ ነበር፡-

> አፍሪካ አንድ አህጉር ነው። በዚህ ታላቅ አህጉር ውስጥ የሚኖሩ ሕዝቦች ለአውሮፓ ታላላቆች ከሌሎች ሕዝቦች ቀዳሚነታቸውን ማረጋገጥ አለባቸው። አውሮፓ ይህን ታላቅ አህጉር ለማስተካከልና በተሻለ መንገድ ለመቅረጽ፣ ሕዝቡንም ወደተሻለ ደረጃ ለማሳደግ የሚያስፈልገውን ታሪካዊ ተግባሩን የመወጣት ፈተና ቀርቦለታል። ይህን ፈተና የመወጣት ተግባሩን በአግባቡ ካከናወነ፤ በአንድ ቃል አንድ ዓለም ለማምጣት እንበቃለን።

ታዋቂው የሰው ዘር አጥኚ ዶ/ር ፌሊክስ ቮን ሉሻአን በሥነ-ሰብ ምርምር ጉባኤ ላይ ነጭ ስላልሆነው ቀለማም የዓለም ሕዝብ የሚከተለውን ብሎ ነበር፡-

> ቀለማም ሰዎችን ወደ ከፍተኛ ደረጃ የማልማት ጉዳይ አይደለም፤ ይልቁንስ የራሳችንን ሰዎች የመጠበቅ እንጂ። ዋናው ቁም ነገር ሌሎቹን ወደ ላይ የማምጣቱ ጉዳይ ሳይሆን፤ እኛ ወደ ታች እንዳንወርድ መጠንቀቅ ነው!

14 በ11ኛው ሰዓት ላይ ጄኔራል ጉስታቭ ሄልብሮንዝ ቮአ ቲሳቢአ በ"ፒተር ሎይድ" መስከረም 11/1935 ሲጽፍ "ጥያቄው አንድን ትውልድ እንዳለ ማቆየት ነው፤ አንገቱን በሱዳን ቀና ያደረገው የጥቁሮች አደገኛ እንቅስቃሴ አምዱርማን ላይ በተገኘው የነጮች ድል ቀዝቀዝ ብሎ ነበር። በሙሶሊኒ እንደታቀደው ለነጮች ጦርነት ጥቁሮችን ቀጥሮ ማሰለፍ የተሻለ ተግባር ነው።"



በኢትዮጵያ መንግሥት የሚደገፈው የወጣት ኢትዮጵያውያን ንቅናቄ በዘዴና በጽናት እየተንቀሳቀሰ፣ በእያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ ኅሊና ውስጥ በነጭ ዘር ላይ ጥላቻን እየዘራ፣ አውሮፓውያን የሚለግሱትን ችሮታ በመጠቀም አውሮፓውያኑን የቅኝ ግዛት ባለቤትነት ለማሳጣት በመንቀሳቀስ ላይ ነው።

* * * *

የኢትዮጵያ መሪዎች በዓለም ታሪክ ላይ ጠባሳውን ትቶ የሚያልፍ ታሪክ ለማስመዝገብ ጉዞ ጀምረዋል። አሁን መምረጥ ያለባቸው አውሮፓውያን በአፍሪካ ውስጥ ባላቸው ተሰሚነት ውስጥ በመካተት በፈቃደኝነት ለሚካሄደው ባህላዊ ልማት እና ሥልጣኔ ታማኝ ተባባሪ መሆን፣ ወይም በማይረባ ቅሬታ እና በተቃወሰ የዘር ጥላቻ መላ ቢስ የሆነውን ፖሊሲ በነጭና በጥቁር ሕዝቦች መኻል የጥላቻ እሳት በማቀጣጠልና ዓለም አቀፉን ሁኔታ በመበከል በመካሄድ ላይ ያለውን ሰላማዊ የሥልጣኔ ሂደት ማኮላሸት ነው።

* * * *

ገዢው የአማራ ብሔር ለውጭ ኃይሎች ያለው ጥላቻ ለሁሉም የውጭ መንግሥታትና ዜጎቻቸው አሳሳቢ ሆኗል።

* * * *

የውጭ ዜጎች ከሀገሬው ጋር በእኩል ደረጃ መስተናገድን ሊተገብሩት ቀርቶ ሊያስቡት እንኳ አይችሉም። ሁሉም ነገር በአድልዎ ስለሚከናወን የውጭ ዜጎች ዝቅ ተደርገው ነው የሚታዩት። በኢትዮጵያ ሕግ መሠረት የውጭ ዜጋ በሀገሪቱ ውስጥ ቋሚ ንብረት ሊያፈራና የቤት ባለቤት ሊሆን ጨርሶ አይችልም። መብቱ ቤት ተከራይቶ መኖር ስለሆነ ማንኛውም ሁኔታ የሚወሰነው በአከራዩ በጎ ፈቃድ ነው። በቤት ሠራተኛ አስተዳደርም የውጭ ዜጋው በቀጠረው አገልጋዩ ላይ እንደሀገሬው መብት ኖሮት ቅጣት ሊጥልበት አይፈቀድለትም።